# የአማርኛ መማሪያ



ለሁለተኛ ክፍል

# የአማርኛ መማሪያ




አዘጋጆች

ተስፋዬ ሸዋዬ

መኰንን ሲሳይ

ከበደ ደስታ


## ለሁለተኛ ክፍል


ሠዓሊው ቦጋለ በላቸው



ትሚ

በትምህርትና ሥነ ጥበብ ሚኒስቴር

በሥርዓተ ትምህርትና መጻሕፍት ዝግጅት

ዋና ፡ ክፍል ፡ ተጻፈ ።

አዲስ አበባ

This is brought to you by
www.binyamhk.wordpress.com

ይህ የቀረበላችሁ በ
www.binyamhk.wordpress.com
ነው።



# ማውጫ

# ማ ሳ ሰ ቢ ያ

በዚህ በአንደኛ የአማርኛ መማርያ መጽሐፍ ውስጥ የሚገኙት ተረቶች አዲሶች አይደሉም ። በየጊዜው በልዩ ልዩ ቦታዎች በቃል የተነገሩና በአንዳንድ መጻሕፍትም ውስጥ የተጠቀሱ ናቸው ። ሆኖም በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የቀረቡት ለንባብ ጀማሪዎች ሊገባ በሚችል ቀላል ቋንቋ ተሳክተው እንጂ በቃል በሚነገሩበት ይዞታ ወይም በአንዳንድ መጻሕፍት ውስጥ በቀረቡበት ዘዴ አይደለም ።

ተረቶቹም ሲመረጡ ለጀማሪዎች አእምሮ ቀላልነታቸው ፣ እጥረታቸውና ትምህርት ሰጪነታቸው ተገምቶ ነው ። የአቀራረባቸውም ቅደም ተከተል ይህንኑ መሠረት ያደረገ ስለሆነ ጀማሪ አንባቢም ተረቶቹን ካነበበ በኋላ ለየተረቶቹ የተሰጡትን መልመጃዎች ቢሠራ የቋንቋ ትምህርቱንና አስተሳሰቡን ለማዳበር ይረዳዋል ።

ይህንን መጽሐፍ ስናዘጋጅ በምክርና በሐሳብ የረዱንን ሁሉ ከልብ እናመሰግናለን ።

አዘጋጆቹ

# የራበው ውሻ

አንድ በጣም የራበው ውሻ የሚበላ ነገር ለመፈለግ ወደ አንድ መንደር ሄደ ። እዚያም ሰዎች በሬ አርደው ሥጋ ሲከፋፈሉ አየና አጠገባቸው ቆመ ።

ከሰዎቹ መካከል አንዱ ለውሻው አዝኖለት የበሬውን ሳንባ ወረወረለት ። ውሻው ሳንባውን ባፉ ይዞ ወደ ጫካ ሮጠ ።

ውሻው ጫካ ውስጥ ሲገባ ኩሬ አይቶ ቆመ ። ወደውኃው ሲመለከት የራሱን መልክ ከውኃው ውስጥ አየ ።

ከዚህ በኋላ ውሻው ሌላ ውሻ ሥጋ ይዞ የቆመ መሰለው ። ስለዚህ ሥጋውን ለመቀማት ፈለገና ለመጮህ አፉን ሲከፍት የያዘው ሳንባ አምልጦት ከውኃው ውስጥ ወደቀበት ፤ በዚህ ምክንያት ምንም ሳይበላ ወደቤቱ ተመለሰ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ

፩/ ውሻው ወደ መንደር የሄደው ለምን ነበር ?

ሀ/ ለሽርሽር
ለ/ የሚበላ ነገር ለመፈለግ
ሐ/ የሚጠጣ ነገር ለመፈለግ
መ/ የቤቱ መንገድ ጠፍቶት

፪/ እመንደሩ ውስጥ ሰዎቹ ምን ያደርጉ ነበር ?

ሀ/ ይጫወቱ ነበር
ለ/ የበሬ ሥጋ ይካፈሉ ነበር
ሐ/ ውሻውን ይጠብቁ ነበር
መ/ ተቀምጠው ነበር

፫/ አንዱ ሰውዬ ለውሻው ምን ሰጠው ?

ሀ/ የበሬውን ሥጋ
ለ/ የበሬውን ልብ
ሐ/ የበሬውን ሳንባ
መ/ የበሬውን ቀንድ

፬/ ውሻው ውኃ ውስጥ ምን አየ ?

ሀ/ የሌላ ውሻ መልክ አየ
ለ/ ምንም አላየ
ሐ/ ሥጋ አየ
መ/ የራሱን መልክ አየ

፭/ ውሻው ምንም ሳይበላ ወደ ቤቱ ለምን ተመለሰ ?

ሀ/ የሚበላው ስላጣ
ለ/ የያዘው ሳንባ ውኃ ውስጥ ስለወደቀ
ሐ/ ስለጠገበ
መ/ ስለታመመ

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ፡፡

፩/ ሰዎች በሬ አርደው ሥጋ . . . . . . . . . . . . አየና . . . . . . . . . . . . . . ቆመ ፡፡
፪/ ከሰዎቹ መካከል አንዱ ለውሻው . . . . . . የበሬውን . . . . . ወረወረለት ፡፡
፫/ ውሻው ሳንባውን . . . . . . . . . . . . ይዞ ወደ . . . . . . . . . . . . . . ሮጠ ፡፡
፬/ ለመጮህ አፉን . . . . . . . . . . የያዘው ሳንባ . . . . . ውኃው ውስጥ ወደቀበት ፡፡

# ሦስት ሞኞች

አንድ ቤት ውስጥ የሚኖሩ ሦስት ሰዎች ነበሩ ። እነዚህም ሰዎች ሥራቸው እርሻ ነበር ። አንድ ቀን የአንደኛው ሰውዬ ሞፈር ተሰበረ ። እመንደራቸው ለሞፈር የሚ ሆን እንጨት የለም ። ወደ ጫካ ሄደው ለሞፈር የሚሆን እንጨት ፈለጉ ። ለሞፈር የሚ ሆን እንጨት ሳያገኙ ማታ ወደቤታቸው ተመለሱ ። በማግስቱም ተነስተው ሞፈር ለመፈለግ ወደ ሌላ ጫካ ሄዱ ።

ከሩቅ አንድ ዛፍ አዩ ። በጣም ደስ አላቸው ። ሦስቱም ሰዎች እየሮጡ ወደ ዛፉ ሄዱ ። እዛፉ አጠገብ ሲደርሱ ዙሪያውን እየዞሩ አዩ ። ዛፉ ገደል አፋፍ ላይ ነበር ። ጥሩ ሞፈር የሚሆን እንጨት አገኘን አሉ ። መቁረጥ ጀመሩ ።

መጥረቢያው ደነዝ ስለሆነ እንጨቱን መቁረጥ አቃታቸው ። ሰዎቹ ቁጭ ብለው ተመካከሩና "ሁለታችን እዛፉ ላይ ወጥተን እናወዛውዘው ። አንዱ ይቁረጥ ' አሉ ። ሁለቱ ሰዎች እዛፉ ላይ ወጡ ። አንዱ ከሥር መቁረጥ ጀመረ ። ከዚያ በኋላ ዛፉ ተቆ ረጠና በገደል ውስጥ ወደቀ ። ሁለቱም ሰዎች ከገደል ውስጥ ገቡ ። የሚቆርጠውም ሰውዬ ሞፈሩን ይዘው ጠፉ አለና ዘሎ አብሮ ገባ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ሦስቱ ሰዎች ወደጫካ ለምን ሄዱ ?

ሀ/ ለአደን
ለ/ ለጨዋታ
ሐ/ እንጨት ለቀማ
መ/ ለሞፈር የሚሆን እንጨት ለመፈለግ

፪/ ሦስቱ ሰዎች ጫካ ውስጥ ምን አገኙ ?

ሀ/ ለሞፈር የሚሆን እንጨት
ለ/ ለቀንበር የሚሆን እንጨት
ሐ/ ለቤት መሥሪያ የሚሆን እንጨት
መ/ ለወንበር የሚሆን እንጨት

፫/ ሦስቱ ሰዎች እንጨቱን መቁረጥ ለምን አቃታቸው ?

ሀ/ መጥረቢያው ደነዝ ስለሆነ
ለ/ ሰዎቹ ስለደከማቸው
ሐ/ እንጨቱ ጠንካራ ስለሆነ
መ/ እንጨቱ ትልቅ ስለሆነ

፬/ ሦስቱ ሰዎች ቁጭ ብለው ምን ተመካከሩ ?

ሀ/ ሌላ እንጨት ለመፈለግ
ለ/ አንደኛው ሲቆርጥ ሁለቱ እንጨቱ ላይ ወጥተው እንዲያወዛውዙት
ሐ/ ሦስቱ ሲቆርጡ አንደኛው እንጨቱ ላይ ወጥቶ እንዲያወዛውዝ
መ/ ሦስቱም እንጨት ላይ ወጥተው እንዲያወዛውዙት

፭/ ሥራቸው እርሻ የሆነ ሰዎች ምን ይባላሉ ?

ሀ/ ገበሬዎች
ለ/ ነጋዴዎች
ሐ/ ሐኪሞች
መ/ ወታደሮች

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ የአንደኛው ሰውዬ . . . . . . . . . . . . . ተሰበረ ።
፪/ እመንደራቸውም ለ . . . . . . የሚሆን . . . . . . . . . . . የለም ።
፫/ በማግሥቱም ተነሥተው . . . . . . . . . ወደሌላ . . . . . . . . . . . . ሄዱ ።
፬/ ዛፉ ገደል . . . . . . . . . . . . . . ላይ ነበር ።
፭/ መጥረቢያው . . . . . . . . . . . ስለሆነ እንጨቱን መቁረጥ አቃታቸው ።

## ለሚከተሉት ጥያቄዎች መልስ ስጥ ።

፩/ ሞፈር የተሰበረበት ገበሬ አንተ ብትሆን ምን ታደርግ ነበር ?
፪/ መጥረቢያው እንዲቆርጥ ምን ማድረግ ያስፈልጋል ?
፫/ ሦስቱም ሰዎች አብረው ወደ ጫካ መሄዳቸው ጥሩ ነው ? ለምን ?
፬/ ይህን የሚመስል ታሪክ ታውቃለህ ? ጻፍና ለጓደኞችህ አንብብላቸው ።

# አውራ ዶሮና ቀበሮ

በጫካ ውስጥ የሚኖር አንድ ቀበሮ ነበር ። ቀበሮው በጣም ራበውና እመንደር ውስጥ ሲዞር አውራ ዶሮ አየ ።

አውራ ዶሮው አጥር ላይ ወጥቶ ኩኩሉ አለ ። ቀበሮውም ወደ ዶሮው ተጠጋ ። "ጥሩ ድምፅ ስላለህ እባክህን እንደገና ኩኩሉ በል" አለው ። አውራ ዶሮውም ደስ አለውና እንደገና ኩኩሉ ሊልለት ዓይኑን ጨፍኖ ጉንበስ አለ ። ቀበሮውም ቶሎ ብሎ ዶሮውን ያዘና ወደጫካ ሮጠ ። እረኞችም ቀበሮውን ተከተሉት ።

አውራ ዶሮው ቀበሮውን እንዲህ አለው ። "እረኞቹ ሊደርሱብህ ነው ። እንዳይገድሉህ የናንተ ዶሮ አይደለም በላቸው ።" ቀበሮውም እውነት መስሎት ለእረኞቹ ለመናገር አፉን ሲከፍት ዶሮው ካፉ አመለጠው ። እረኞቹም ዶሮውን ይዘው ወደቤት ተመለሱ ።



# መ ል መ ጃ

## ተስማሚውን መልስ ምረጥ ።

፩. ቀበሮው የሚኖረው የት ነው ?

ሀ/ ጫካ ውስጥ
ሐ/ ከተማ ውስጥ
ለ/ ሜዳ ላይ
መ/ መንደር ውስጥ

፪/ ቀበሮው እመንደር ውስጥ ሲዞር ምን አየ ?

ሀ/ አህያ
ሐ/ ላም
ለ/ ዶሮ
መ/ ፍየል

፫. ቀበሮው አውራ ዶሮውን ምን አለው ?

ሀ/ ጥሩ ድምፅ ስላለህ ጓደኛ እንሁን
ለ/ ጥሩ ድምፅ ስላለህ ዝፈንልኝ
ሐ/ ጥሩ ድምፅ ስላለህ ኩኩሉ በልልኝ
መ/ ጥሩ ድምፅ ስላለህ ጐበዝ ነህ

፬ አውራ ዶሮው ዓይኑን ጨፍኖ ጐንበስ ያለው ለምንድን ነው ?

ሀ/ ለመዝፈን
ሐ/ ቀበሮውን ለመጥራት
ለ/ ለመጮህ
መ/ ኩኩሉ ለማለት

፭/ ቀበሮው ዶሮውን ምን አደረገው ?

ሀ/ በላው
ሐ/ ነከሰው
ለ/ ይዞት ወደ ጫካ ሮጠ
መ/ ክንፉን ቆረጠው

፮/ አውራ ዶሮው ከቀበሮው አፍ እንዴት አመለጠ ?

ሀ/ ክንፉ ተቆረጠ
ሐ/ እረኞች ቀበሮውን ሲደርሱበት
ለ/ ቀበሮው አፉን ሲከፍት
መ/ አላመለጠም

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ በጫካ ውስጥ . . . . . . . . . . . አንድ ቀበሮ ነበር ።
፪/ ቀበሮው በጣም . . . . . . . . . . . መንደር ውስጥ . . . . . . አውራ ዶሮ አየ ።
፫/ አውራ ዶሮው አጥር ላይ ወጥቶ . . . . . . . . . . . . . አለ ።
፬/ ቀበሮውም ወደ ዶሮው . . . . . . . . . . . ።
፭/ ጥሩ ድምፅ . . . . . . . . . . . እባክህን እንደገና . . . . . . . . . . . በል አለው ።
፮/ አውራ ዶሮውም ደስ አለውና . . . . . . . . . ኩኩሉ ሊልለት ዓይኑን . . . . . ጐንበስ አለ ።
፯/ ቀበሮውም . . . . . . . . . . ብሎ ዶሮውን ያዘና ወደ . . . . . . . . . . . ሮጠ ።
፰/ እረኞችም ቀበሮውን . . . . . . . . . . . . . ።
፱/ አውራ ዶሮው ቀበሮውን እንዲህ አለው እረኞቹ . . . . . . . . . . . ነው ።

. . . . . . . . . . .  . . . . የናንተ ዶሮ አይደለም በላቸው ።

፲/ ቀበሮው ለእረኞቹ ለመናገር አፉን . . . . . . ዶሮው . . . . . . አመለጠው ።

፲፩/ እረኞቹም ዶሮውን . . . . . . . . . . . ወደቤት ተመለሱ ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ አንተ ቀበሮውን ብትሆን ምን ታደርግ ነበር ?

፪/ አንተ ዶሮውን ብትሆን ኖሮ ምን ታደርግ ነበር ?

፫/ አንተ ከእረኞቹ አንዱን ብትሆን ኖሮ ምን ታደርግ ነበር ?

፬/ ዶሮ ኩኩሉ የሚለው ለምንድነው ?

፭/ ዶሮዎችን አውሬ እንዳይበላቸው ምን ማድረግ ያስፈልጋል ?



# የዔሊና የጥንቸል ውድድር

ዔሊ ስትሄድ አይታችኋል ? በጣም ቀርፋፋ ናት ። አካላቷ ስለሚከብዳት ቶሎ ቶሎ መሄድ አትችልም ። ጥንቸልስ ? ጥንቸል በጣም ትሮጣለች ። ውሻ እንኳን ቢያባርራት ለማምለጥ ትችላለች ።

አንድ ቀን ዔሊና ጥንቸል እመንገድ ተገናኙ ። ጥንቸልም ዔሊን "አንቺ ቀርፋፋ ወዴት ትሄጃለሽ ?" አለቻት ። ዔሊም ተናደደችና "ለምን ቀርፋፋ ትይኛለሽ ? ከፈለግሽ ነይ በሩጫ እንወዳደር" አለቻት ። ጥንቸልዋም እሺ አለቻትና በሩጫውም ቦታ ተስማሙ ። ቀበሮንም ዳኛ አደረጉት ። ከዚህ በኋላ ቀበሮ አንድ ሁለት ሦስት አለና ሩጫው ተጀመረ ።

ጥንቸል በአንድ ጊዜ ዔሊን ቀደመቻት ። ዔሊ ግን በጣም ወደኋላ ቀረች ። ጥንቸልም ዘወር ብትል ዔሊን ስትንቀረፈፍ አየቻት ። ጥንቸልም ዔሊን ልጠብቃት አለችና እሣር ላይ ጋደም አለች ። በዚህም ጊዜ እንቅልፍ ወሰዳት ።

ዔሊ ቀስ እያለች ስትሄድ እውድድሩ ሥፍራ ደረሰች ። ተመልካቾችም ለዔሊ ሲያጨበጭቡላት ጥንቸልዋ ከእንቅልፍዋ ነቃች ። ጥንቸልዋም በጣም ተናደደች ። መሸነፍዋንም ዐውቃ ዔሊን "ሁለተኛ አልሰድብሽም" አለቻት ።



# መ ል መ ጃ

የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ዔሊ ቶሎ ቶሎ የማትሄደው ለምንድን ነው ?

ሀ/ እግርዋ አጭር ስለሆነ

ለ/ ቶሎ ቶሎ መሄድ ስለማትወድ

ሐ/ አካላቷ ስለሚከብዳት

መ/ ቀርፋፋ ስለሆነች

፪/ ዔሊና ጥንቸል የት ተገናኙ ?

ሀ/ እመንገድ ላይ

ለ/ እጫካ ውስጥ

ሐ/ እሩጫ ሜዳ

መ/ እቤታቸው ውስጥ

፫/ ጥንቸል ዔሊን ምን ብላ ሰደበቻት ?

ሀ/ ደካማ

ለ/ ቀልቃላ

ሐ/ ቀርፋፋ

መ/ እንቅልፋም

፬/ ዔሊ ጥንቸልን ምን አለቻት ?

ሀ/ መልሳ ሰደበቻት

ለ/ ነዪ እሩጫ እንወዳደር አለቻት

ሐ/ ዝም ብላት ሄደች

መ/ ያልሽውን አልሰማሁም አለቻት

፭/ ዔሊና ጥንቸል ዳኛ ያደረጉት ማንን ነው ?

ሀ/ ውሻን

ለ/ ጅብን

ሐ/ ዝንጀሮን

መ/ ቀበሮን

፮/ መጀመሪያ በሩጫ ማን ቀደመ ?

ሀ/ ዔሊ

ለ/ ጥንቸል

ሐ/ እኩል ነበሩ

መ/ ቀበሮ

፯/ ጥንቸል እሣር ላይ ለምን ተኛች ?

ሀ/ ደክሟት

ለ/ ሩጫውን ስለጨረሰች

ሐ/ ዔሊን ለመጠበቅ

መ/ እንቅልፍ ስለያዛት

፰/ ጥንቸልዋ ከእንቅልፍዋ እንዴት ነቃች ?

ሀ/ ተመልካቾች ተነሺ ብለው ሲያጨበጭቡላት

ለ/ ተመልካቾች ዔሊ ስላሸነፈች ሲያጨበጭቡላት

ሐ/ ዔሊ ባጠገብዋ ስታልፍ

መ/ እንቅልፍዋን ስለጨረሰች

፱/ ጥንቸልዋ በሩጫ ስትሸነፍ ምን ሆነች ?

ሀ/ አለቀሰች

ለ/ ሳቀች

ሐ/ ተናደደች

መ/ ተደሰተች

፲/ ጥንቸልዋ ዔሊን ምን አለቻት ?

ሀ/ ሁለተኛ አልሰድብሽም

ለ/ ጐበዝ ነሽ

ሐ/ እንደገና እንሩጥ

መ/ ዝም

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ ዔሊ በጣም . . . . . . . . . . . . . ናት ።
፪/ አካላትዋ . . . . . . . . . . ቶሎ ቶሎ መሄድ አትችልም ።
፫/ ጥንቸል . . . . . . . . . . . . . . ትሮጣለች ።
፬/ ውሻ እንኳን ቢያባርራት . . . . . . . . . . . . . . ትችላለች ።
፭/ ዔሊና ጥንቸል . . . . . . . . . . . . . ተገናኙ ።
፮/ ጥንቸልም ዔሊን “አንቺ . . . . . . . . . . ወዴት . . . . . . . . . . . .” አለቻት ።
፯/ ዔሊም ተናደደችና “ለምን . . . . . . . . . ትይኛለሽ ?
፰/ ከፈለግሽ ነይ . . . . . . . . እንወዳደር” አለቻት ።
፱/ በ . . . . . . . . . . ቦታ ተስማምተው ቀበሮን . . . . . . . . . . . . አደረጉት ።
፲/ ቀበሮም አንድ . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . አለና . . . . . . . . . . ተጀመረ ።
፲፩/ . . . . . . . . . . . . . በአንድ ጊዜ . . . . . . . . . . ቀደመቻት ።
፲፪/ . . . . . . . . . . . . በጣም ወደኋላ ቀረች ።
፲፫/ ጥንቸልም ዘወር ብትል . . . . . . . . . . . ስትንቀረፈፍ አየቻት ።
፲፬/ ጥንቸልም ዔሊን . . . . . . . . . አለችና እሣር ላይ . . . . . . . . . አለች ።
፲፭/ . . . . . . . . . . . . ቀስ እያለች ስትሄድ . . . . . . . . . ሥፍራ ደረሰች ።
፲፮/ ተመልካቾቹም ለ . . . . . . . ሲያጨበጭቡላት . . . . . . . . . ከእንቅልፍዋ ነቃች ።
፲፯/ . . . . . . . . . . “ሁለተኛ አልሰድብሽም” አለቻት ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ጥንቸልና ዔሊ እመንገድ ላይ ሲገናኙ ጥንቸል ዔሊን ሰደበቻት ።
አንተ እመንገድ ላይ የምታውቀውን ተማሪ ብታገኝ ምን ትለዋለህ ?
፪/ አጫዋች ሆነህ ታውቃለህ ? አንተና ጓደኞችህ ስትጫወቱ አጫዋቹ ማን ነበር ?
፫/ ጥንቸል ዔሊን ልጠብቃት አለችና እሣር ላይ ጋደም አለች ። እንቅልፍ ወሰዳት ።
በሩጫ ዔሊ ቀደመቻት ። አንተ ጥንቸልዋን ብትሆን ምን ታደርግ ነበር ?

# አንበሳና አይጥ

አንድ አንበሳ በጣም ራበውና ጫካ ውስጥ ሲሆር በሬ አገኘ ። በሬውንም ገድሎ በላና ሲጠግብ ወደጎሬው ሄዶ ተኛ ። እንቅልፍም ወሰደው ።

አንዲት አይጥ አንበሳው ጕሬ ውስጥ ስትዘዋወር አንበሳውን ነካችውና አንበሳው ከእንቅልፉ ነቃ ። ለምን ቀሰቀስሽኝ ብሎ አይጥዋን በጣም ተቆጣት ። ከመሬትም ብድግ አደረጋትና ዓይኑን አፈጠጠባት ። አይጥዋም በጣም ፈራችና ዓይንዋን ቁልጭ ቁልጭ ታደርግ ጀመረ ።

በኋላም እያለቀሰች "እባክዎን አይግደሉኝ ። አንድ ቀን እረዳዎታለሁ" አለችው ። "አንቺ ደግሞ ምን ትረጅኛለሽ?" አለና አንበሳው በጣም ተቆጣ ። አይጥዋም "እባክዎን ጌታዬ ይማሩኝ" አለችው ። አንበሳውም አሳዘነችውና ለቀቃት ።

አንድ ቀን አንበሳው በገመድ ወጥመድ ተያዘ ። ከወጥመዱም ለማምለጥ ስላል ቻለ ይጮህ ነበር ። በዚህ ጊዜ ያቺ አይጥ ሰማችና ወደ አንበሳው ሄዳ "ጌታዬ ምን ሆኑ?" አለችው ። "በወጥመድ ተይዠለሁ" አላት ። አይጥዋም "አይዞዎት" አለችና ወጥመዱን በጥርስዋ መቁረጥ ጀመረች ። ወጥመዱን ብዙ ቦታ በጣጠሰችውና አንበሳውም ከወጥመዱ ወጣ ። አንበሳውም ደስ ብሎት አመሰገናት ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ አንበሳው በሬ ከየት አገኘ ?

ሀ/ ከበረት — ሐ/ ከጫካ

ለ/ ከመንደር — መ/ ከከተማ

፪/ አንበሳው ያገኘውን በሬ ምን አደረገው ?

ሀ/ ወደጎሬው ወሰደው — ሐ/ አጫወተው

ለ/ በላው — መ/ ወደቤቱ ወሰደው

፫/ አንበሳው ከእንቅልፉ ለምን ነቃ ?

ሀ/ አይጥ ስለነካችው — ሐ/ ስለራበው

ለ/ እንቅልፉን ስለጨረሰ — መ/ ስለደከመው

፬/ አንበሳው አይጥዋን ከመሬት ብድግ አድርጎ ምን አደረጋት ?

ሀ/ ገደላት — ሐ/ ቆነጠጣት

ለ/ ዓይኑን አፈጠጠባት — መ/ ወረወራት

፭/ አይጥዋ ፈርታ ምን አደረገች ?

ሀ/ ሮጠች — ሐ/ ሳቀች

ለ/ አለቀሰች — መ/ ዓይንዋን ቁልጭ ቁልጭ አደረገች

፮/ አይጥዋ እያለቀሰች ምን አለች ?

ሀ/ እባክዎን ይልቀቁኝ — ሐ/ እባክዎ አይግደሉኝ አንድ ቀን እረዳዎታለሁ ።

ለ/ እባክዎን አይግደሉኝ — መ/ እባክዎን ቶሎ ይግደሉኝ

፯/ አንበሳው አይጥዋን ለምን ለቀቃት ?

ሀ/ ስላለቀሰች — ሐ/ ስላሳዘነችው

ለ/ ስለለመነችው — መ/ ስለፈራት

፰/ አይጥዋ አንበሳውን እንዴት አድርጋ ከወጥመድ ውስጥ አወጣችው ?

ሀ/ ወጥመዱን በጥርስዋ በጥሳ — ሐ/ ወጥመዱን በእጅዋ በጥሳ

ለ/ ወጥመዱን በቢላዋ ቆርጣ — መ/ ወጥመዱን በእሳት አቃጥላ

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ አንድ አንበሳ በጣም . . . . . . . . . ጫካ ውስጥ . . . . . . . . . . በሬ አገኘ ።

፪/ በሬውንም ገድሎ በላና . . . . . . . . . . . . . . ወደ ጐሬው ሄዶ ተኛ ።

፫/ አንዲት አይጥ አንበሳው ጐሬ ውስጥ . . . . . . . . አንበሳውን ነካችውና አንበ ሳው . . . . . . . . . ነቃ ።

፬/ ለምን . . . . . . . . . ብሎ አይጥዋን በጣም ተቆጣት ።

፭/ ከመሬት . . . . . . . . . . . አደረጋትና ዓይኑን . . . . . . . . . . ።

፮/ አይጥዋም በጣም . . . . . . . . ዓይንዋን ቁልጭ . . . . . . . . . . ጀመር ።
፯/ በኋላም እያለቀሰች . . . . . . . . . አይግደሉኝ አንድ ቀን . . . . . . . አለችው ።
፰/ አንቺ ደግሞ ምን . . . . . . . . አለና አንበሳው በጣም ተቆጣ ።
፱. አይጥዋም እባክዎን ጌታዬ . . . . . . . አለችው አንበሳውም . . . . . ለቀቃት ።
፲/ አንድ ቀን አንበሳው በገመድ . . . . . . . . . . ተያዘ ።
፲፩/ በዚህን ጊዜ ያች አይጥ . . . . . . . . . ወደ አንበሳው ሄዳ . . . . . . . . ምን
ሆኑ አለችው ።
፲፪/ . . . . . . . . . . ተይገፐለሁ አላት ።
፲፫/ አይጥዋም . . . . . . . . . . . አለችና . . . . . . . . . . በጥርስዋ መቁረጥ ጀመረች ።
፲፬/ . . . . . . . . . . . ብዙ ቦታ . . . . . . . . . . . አንበሳው ከወጥመዱ ወጣ ።
፲፭/ አንበሳውም ደስ ብሎት . . . . . . . . . ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩ በግህ በወጥመድ ቢያዝብህ እንዴት ታድነዋለህ ?
፪ ወጥመድ ለምን ያገለግላል ?
፫ የአንበሳውንና የአይጥዋን ታሪክ ለጓደኞችህ ንገራቸው ።
፬ አንተ አንበሳውን ብትሆን ከወጥመዱ ለመውጣት ምን ታደርግ ነበር ?
፭ አንተ አንበሳውን ብትሆን ለአይጥዋ ምን ታደርግላት ነበር ?



# ጦጣና ተማሪ

በአንድ አገር ውስጥ አንድ ጥሩ ትምህርት ቤት ነበር ። ተማሪዎችም ከየቦታው እየ መጡ ይማሩበት ነበር ። አንድ ጐበዝ ልጅ ለመማር እዚህ ትምህርት ቤት ገባ ። ይህም ተማሪ የሚጽፈውና የሚያጠናው በአንድ ዛፍ ሥር ነበር ።

አጥንቶ ሲደክመው ደብተሩንና ብዕሩን እዛፉ ሥር ትቶ ወደ ጨዋታ ይሄዳል ። ከጨዋታ ሲመለስ ደብተሩ ተሞነጫጭሮበት ያገኘዋል ። ተማሪውም በዚህ ነገር በጣም ይናደድ ነበር ።

ማን እንደሚሞነጫጭርበት ለማወቅ አንድ ቀን ከዛፍ ላይ ወጥቶ ይጠብቅ ጀመረ ። አንዲት ጦጣ መጥታ እንደርሱ ለመጻፍ ደብተሩን ስታገላብጥና ስትሞነጫጭር አየ ። የጦጣዋም ሥራ በጣም ስላናደደው እቤቱ ሄዶ ቢላዋ ይዞ መጣ ። ከዚያም በኋላ በዛፉ ሥር ተቀምጦ ጻፈና ከቤት ያመጣውን ቢላዋ አነሣ ። በደንደሱ በኩል አንገቱን ከርክሮ ወደ ጨዋታ ሄደ ። በዚህ ጊዜ ጦጣዋ ተማሪው ወደ ጨዋታ መሄዱን አይታ ደብተሩን ትሞነጫጭር ጀመር ። ቀጥላም እንደ ተማሪው አደርጋለሁ ብላ አንገትዋን በቢላዋ ቆርጣ ወደቀች ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ተማሪው የሚያጠናው የት ነበር ?

ሀ/ እቤት ውስጥ
ለ/ እቤት ሥር
ሐ/ እዛፍ ሥር
መ/ እዛፍ ላይ

፪/ ተማሪው አጥንቶ ሲደክመው ደብተሩንና ብዕሩን የት አስቀመጠ ?

ሀ/ እዛፍ ሥር
ለ/ እኪሱ ውስጥ
ሐ/ እሣጥኑ ውስጥ
መ/ እቦርሳው ውስጥ

፫/ ተማሪው አጥንቶ ሲደክመው ወዴት ይሄድ ነበር ?

ሀ/ ወደቤቱ
ለ/ ወደጨዋታ
ሐ/ ወደተማሪ ቤት
መ/ ወደ ወንዝ

፬/ ተማሪው ከጨዋታ ሲመለስ ደብተሩ ምን ሆኖ ያገኝዋል ?

ሀ/ ታጥፎ
ለ/ ተቀድዶ
ሐ/ ተሞነጫጭሮ
መ/ ተቀምጦ

፭/ ተማሪው እዛፍ ላይ ወጥቶ ምን አየ ?

ሀ/ ጦጣዋ ደብተሩን ስትበላ
ለ/ ጦጣዋ እንደርሱ ለመጻፍ ደብተሩን ስታገላብጥ ?
ሐ/ ጦጣዋ ብዕሩን ስትሰብር
መ/ ጦጣዋ ደብተሩን ስትቀድ

፮/ ተማሪው እቤቱ ሄዶ ምን ይዞ መጣ ?

ሀ/ ዱላ
ለ/ ቢላዋ
ሐ/ መጥረቢያ
መ/ ጎራዴ

፯/ ተማሪው ያመጣውን ቢላዋ ምን አደረገበት ?

ሀ/ ጦጣዋን መታበት
ለ/ ዛፉን ቆረጠበት
ሐ/ በደንደሱ በኩል አንገቱን ከረከረበት
መ/ በስለቱ በኩል አንገቱን ከረከረበት

፰/ ጦጣዋ ለምን ወደቀች ?

ሀ/ ተማሪውን ፈርታ
ለ/ ቢላዋው ስለመታት
ሐ/ አንገትዋን ስለቆረጠች
መ/ በደብተሩ ላይ ስለጻፈች

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ በአንድ አገር ውስጥ . . . . . . . . . . . ጥሩ . . . . . . . . . . . ቤት ነበር ።
፪/ ተማሪዎችም . . . . . . . . እየመጡ ይማሩበት ነበር ።
፫/ አንድ . . . . . . . . ልጅ . . . . . . . . እዚህ ትምህርት ቤት ገባ ።
፬/ ይህም ተማሪ . . . . . . . . የሚያጠናው በአንድ . . . . . . . . ሥር ነበር ።

፫/ አጥንቶ ሲደክመው ደብተሩንና ........ እዛፉ ሥር ትቶ ወደ ........ ይሄዳል ።

፬/ ከጨዋታ .......... ደብተሩ .......... ያገኘዋል ።

፭/ ማን .............. ለማወቅ አንድ ቀን በሌላ ዛፍ ላይ ወጥቶ ........ ጀመረ ።

፮/ አንዲት ጠጣ መጥታ ........... ለመጻፍ ደብተሩን ..........ስት ሞነጫጭር አየ ።

፱/ የጠጣዋም ሥራ በጣም .......... እቤቱ ሄዶ .......... ይዞ መጣ ።

፲/ በዛፉ ሥር ተቀምጦ .......... ከቤት ያመጣውን ቢላዋ አነሣ ።

፲፩/ .......... በኲል አንገቱን ከርክሮ ወደ ........... ሄደ ።

፲፪/ ............ እንደተማሪው .......... ብላ አንገትዋን በቢላዋ ቆርጣ ወደቀች ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ የአንተን ደብተር ጠጣ ብታበላሽብህ ምን ታደርጋለህ ? ታናሽ ወንድምህ ቢያበላ ሽብህስ ?

፪/ መጽሐፍህና ደብተርህ እንዳይበላሹብህ ምን ማድረግ አለብህ ?

፫/ አሁን የጠጣዋንና የተማሪውን ታሪክ አንብበሃል ። እስቲ ለጓደኞችህ ንገ ራቸው ።

፬/ ጠጣዋ የአንተ ብትሆን ኖሮ ተማሪውን ምን ታደርገው ነበር ?

# ማሞ ነጋዴው

ማሞ ነጋዴ ነበር ። አንድ ቀን ዐሥር አህዮች ጭኖ ወደ ንግድ ሄደ ። ብዙ መንገድ በእግሩ ከሄደ በኋላ ደከመውና አንድዋ አህያ ላይ ተቀምጦ ሌሎቹን ይነዳ ጀመረ ። እራቱ የሚሄዱትንም አህዮች ቢቆጥራቸው ዘጠኝ ብቻ ሆኑ ። በዚህ ጊዜ ደንግጦ ከተቀመጠበት አህያ ወረደና የጠፋችውን ለመፈለግ ወደጫካ ሮጠ ። ነገር ግን አህያዋን አጣት ።

ከዚህ በኋላ ማሞ አህያዩ ጠፋች ብሎ በጣም ደነገጠ ። እንደገና ደግሞ ቢቆጥር ዐሥር ሆኑ ። በጣም ደስ አለውና አንደኛዋ ላይ ተቀምጦ ጉዞውን ቀጠለ ። አሁንም አህዮቹን ቢቆጥር ዘጠኝ ሆኑ ። ማሞ በጣም ተናደደ ከአህያዋ ላይ ወረደና ለመፈለግ ወደጫካ ሮጠ ። ምንም ሌላ አህያ አላገኘም ። እሱም በጣም አዝኖ ወደ አህዮቹ ተመለሰና ቢቆጥራቸው ዐሥር ሆኑ ።

ማሞ በእግሬ መሄድ ይሻለኛል ብሎ በእግሩ ሲሄድ አየለን አገኘው ። አየለም "በጣም ደክሞህ ለምን በእግርህ ትሄዳለህ ? አንድዋ አህያ ላይ ለምን አትቀመጥም ?" ብሎ ጠየቀው ። ማሞም "አህያ ላይ ስቀመጥ አንድዋ አህያ ትጠፋብኛለች" አለው ። አየለም "አሁን አንተ ተቀመጥ እንዳትጠፋብህ እኔ እጠብቅልሃለሁ" አለው ።

ማሞ አህያዋ ላይ ተቀምጦ መቁጠር ጀመረ ። "አሁንም ዘጠኝ ብቻ ሆኑ" ብሎ አየለን ተቈጣው ። አየለም ሳቀና "የተቀመጥክባትን አህያ ጭምር ቁጠር" አለው ። ማሞም የተቀመጠባትን አህያ ጨምሮ ቢቆጥር አህዮቹ ዐሥር ሆኑ ። በዚህም ጊዜ ማሞ ደስ ብሎት ጉዞውን ቀጠለ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ማሞ ምን ነበር ?

ሀ/ ገበሬ | ሐ/ ነጋዴ
ለ/ ሐኪም | መ/ አስተማሪ

፪/ ማሞ ስንት አህዮች ነበሩት ?

ሀ/ ዘጠኝ | ሐ/ ስምንት
ለ/ ዐሥር | መ/ ሰባት

፫/ ማሞ አንድዋ አህያ ላይ ለምን ተቀመጠ ?

ሀ/ ስለደከመው | ሐ/ ብዙ መንገድ ስለሄደ
ለ/ አህያዋ እንዳትጠፋበት | መ/ እግሩን ስላመመው

፬/ ማሞ አህያዋን ለመፈለግ ስንት ጊዜ ወደጫካ ሮጠ ?

ሀ/ አንድ ጊዜ | ሐ/ ሦስት ጊዜ
ለ/ ሁለት ጊዜ | መ/ አራት ጊዜ

፭/ የማሞ አህዮች ዘጠኝ የሆኑበት ምክንያት ምንድነው ?

ሀ/ የተቀመጠባትን ስለማይቆጥር | ሐ/ አንድዋ አህያ ስለምትጠፋ
ለ/ ቁጥር ስለማይችል | መ/ አህያዋ ጫካ ውስጥ ስለምትገባ

፮/ ማሞ በመጨረሻ በምን ሄደ ?

ሀ/ በእግሩ | ሐ/ በባቡር
ለ/ በመኪና | መ/ በአህያ

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ ማሞ . . . . . . . . . . . . ነበር ።
፪/ አንድ ቀን . . . . . . . . . . . አህዮች ጭኖ ወደ . . . . . . . . . . . . ሄደ ።
፫/ ብዙ መንገድ . . . . . . . . . . . ከሄደ በኋላ . . . . . . . . . አንድዋ አህያ ላይ ተቀምጦ ሌሎቹን ይነዳ ጀመር ።
፬/ እፊቱ የሚሄዱትንም አህዮች . . . . . . . . . . ዘጠኝ ብቻ ሆኑ ።
፭/ ማሞ በጣም . . . . . . . . . ከአህያዋ ላይ . . . . . ለመፈለግ ወደ ጫካ ሮጠ ።
፮/ ማሞ በእግሬ . . . . . . ይሻለኛል ብሎ በእግሩ . . . . . . አየለን አገኘው ።
፯/ አየለም "በጣም . . . . . . . . . ለምን በእግርህ . . . . . . . . . ." አለው ።
፰/ ማሞም "አህያ ላይ . . . . . . . . . አንዷዋ አህያ . . . . . . . . . . ." አለው ።
፱/ አየለም "አሁን አንተ . . . . . . . . . . . እኔ . . . . . . . . . ." አለው ።
፲/ ማሞ አህያዋ ላይ ተቀምጦ . . . . . . . . . . . ጀመረ ።
፲፩/ አሁንም . . . . . . . . . . . . ብቻ ሆኑ ብሎ አየለን . . . . . . . . . . ።

፲፪/ አየለም ሳቀና “ . . . . . . . . . . . አህያ . . . . . . . . . ቁጠር” አለው ።
፲፫/ ማሞም . . . . . . . . . . . አህያ ጨምሮ . . . . . . . . . አህዮቹ ዐሥር ሆኑ ።
፲፬/ ማሞ ደስ ብሎት . . . . . . . . . . . . . ቀጠለ ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ አንተ ማሞን ብትሆን ኖሮ ምን ታደርግ ነበር ?
፪/ የዚህ ዓይነት ሞኝነት እንዳይደርስብህ ምን ማድረግ ያስፈልግሃል ?



# ዓሣ በውኃ ውስጥ ለምን ይኖራል ?

ድሮ ዓሣ እንደ ሌሎቹ ፍጥረታት ሁሉ በመሬት ላይ ይኖር ነበር ። ዓሣ ወሬኛ ስለነ በረ ሌሎቹን እንስሳት ማማት በጣም ይወድ ነበር ። ወሬ በማመላለስም አንዱን ከአ ንዱ ያጣላ ነበር ።

በጫካ የሚገኙት አውሬዎች ሁሉ ተሰብስበው ሊገድሉት ተማከሩ ። ብዙ ጊዜም ሲፈልጉት አጡትና በጣም ተናደዱ ። በመጨረሻ ግን ያዙትና ክፉ የሚናገርበትን ምላ ሱን በአፉ ውስጥ አጣብቀው ሰፉት ። በኋላም ይህ ብቻ ስለማይበቃው ይገደል አሉና ወደ ወንዝ አፋፍ ወሰዱት ።

እወንዙም አፋፍ ደርሶ የሚገደልበት ሰዓት እስኪደርስ ድረስ መሬት ላይ አስቀ መጡት ። አውሬዎችም ተቀምጠው እንዴት አድርገን እንግደለው እያሉ ሲነጋገሩ ቀኑ ጨለመ ፤ ዓሣውም ቀስ ብሎ ተደብቆ ወደ ወንዙ ውስጥ ገባና አመለጠ ። ከዚያም ጊዜ ጀምሮ ውኃ ጥሩ የመደበቂያ ቦታ ስለሆነለት በዚያው ይኖራል ። ወደ ቀድሞ መኖሪ ያው ወደ መሬትም አልተመለሰም ።

ያ ወሬኛ ምላሱም ተጣብቆ ስለተሰፋ ሊለፈልፍ አይችልም ። ድምጹም አይሰ ማም ። ምላስም ስለሌለው ውኃ ውስጥ ስለሚኖሩት ስለሌሎች ፍጥረቶች ሊያወራ አይ ችልም ። ስለዚህ ሁሉም በሰላም ይኖራሉ ።

## መ ል መ ጃ

የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ድሮ ዓሣ የሚኖረው የት ነበር ?
- ሀ/ በሰማይ ላይ
- ለ/ በመሬት ውስጥ
- ሐ/ በመሬት ላይ
- መ/ በጫካ ውስጥ

፪/ ዓሣ አንዱን ከአንዱ የሚያጣላው እንዴት ነበር ?
- ሀ/ እውነት በመናገር
- ለ/ ወሬ በማመላለስ
- ሐ/ ዱላ በመስጠት
- መ/ በማጫወት

፫/ በጫካ ውስጥ የሚገኙት አውሬዎች ዓሣን ምን አደረጉት ?
- ሀ/ ምላሱን አጣብቀው ሰፉት ።
- ለ/ ገደል ውስጥ ወረወሩት ።
- ሐ/ ወንዝ ውስጥ ጨመሩት ።
- መ/ ገደሉት ።

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

እወንዙም . . . . . ደርሶ የሚገደልበት ሰዓት . . . . . . . . . . ድረስ መሬት ላይ አስቀ መጡት ። አውሬዎቹም . . . . . . . . . . . . እንዴት አድርገን . . . . . . . . . . . . . እያሉ ሲነጋገሩ ቀኑ . . . . . . . . . . . . . ። ዓሣውም . . . . . . . . . . . . ብሎ ተደብቆ ወደ ወንዙ ገባና . . . . . . . . . . . . . . ። ከዚያም ጊዜ ጀምሮ ውኃ ጥሩ . . . . . . . . . . . . . . . . ቦታ ስለሆነለት . . . . . . . . . . . . . . ይኖራል ። ወደ . . . . . . . . . . . . መኖሪያው ወደ መሬ ትም . . . . . . . . . . . . . . . . . ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ወሬ ማመላለስ ማለት ምን ማለት ነው ?
፪/ ወሬ እያመላለሰ የሚያጣላ ጓደኛ ቢኖርህ ምን ታደርገዋለህ ?
፫/ ዓሣ ከውኃ ውስጥ ቢወጣ ምን ይሆና ል ?

# አንዲት ልጅና የማሰሮ ወተት

በአንድ ገበሬ ቤት የምትሠራ አንዲት ልጅ ነበረች ። አንድ ቀን ገበሬው በማሰሮ ወተት ሞላና "ሸጠሽ ገንዘቡን ውሰጂ" አላት ።

በዚህም ጊዜ ልጅቱ በጣም ደስ አላት ። ያን ወተት የሞላ ማሰሮ በራስዋ ላይ አስ ቀምጣ ለመሸጥ ወደ ገበያ ይዛ ሄደች ። በመንገድ ላይ እንዳለችም እንዲህ ስትል አሰ በች ። "እንግዲህ ይህን ወተት ሸጬ ገንዘብ አገኛለሁ ፤ በገንዘቡም ዶሮ እገዛለሁ ፤ ዶሮዋም እንቁላል ትጥልልኛለች ፤ እንቁላሉንም አስፈለፍልና ብዙ ዶሮዎች አገኛ ለሁ ። እነዚያንም ዶሮዎች ሸጬ በማገኘው ገንዘብ ጥሩ ልብስ እገዛለሁ ።

"ያንን አዲስ ልብስ ስለብስ ከሌሎቹ ልጆች የበለጠ ቆንጆ እሆናለሁ ። ስለዚህ ልጆቹ ሁሉ ከእኔ ጋር መጫወት ይፈልጋሉ ፤ እኔ ግን እንቢ እላቸዋለሁ ።

"ለጭፈራ ወደ መንደር ስሄድም አዲሱን ልብሴን እለብሳለሁ ። በዚያን ጊዜ ወጣ ቶች ሁሉ ከእኔ ጋር ለመጨፈር ይፈልጋሉ ። ነገር ግን እኔ እሺ አልላቸውም ። አብ ረን እንጨፍር ብለው የጠየቁኝም እንደሆነ ፊቴን እንዲህ እመልሳለሁ" ብላ አንገት ዋን መለስ ስታደርግ ራስዋ ላይ የነበረው የወተት ማሰሮ ወድቆ ተሰባበረ ። በውስጡ የነበረውም ወተት እሜዳ ላይ ፈሰሰ ። በዚህ ምክንያት ወተቱን ሸጣ ገንዘብ ሳታገኝ ቀረች ።

## መ ል መ ጃ

የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ገበሬው ልጅቷን ምን አላት ?

ሀ/ ገንዘብ ውሰጂ

ለ/ ወተት ሸጪ

ሐ/ ወተት ሸጠሽ ገንዘቡን ውሰጂ

መ/ በማሰሮ ወተት ጨምሪ

፪/ ልጅትዋ ወደ ገበያ ለምን ሄደች ?

ሀ/ ማሰሮ ለመሸጥ

ለ/ ወተት ለመሸጥ

ሐ/ ዶሮ ለመሸጥ

መ/ ልብስ ለመግዛት

የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ልጅትዋ ወደ ገበያ ስትሄድ ያሰበችውን ሁሉ ለጓደኞችህ ንገራቸው ።

፪/ አንተ ልጅትዋን ብትሆን ኖሮ ምን ታደርግ ነበር ?

፫/ ልጅትዋ ሞኝ ናት ወይስ ብልጥ ? ለምን ?

፬/ አንተ ገበሬውን ብትሆን ኖሮ ልጅቷን ምን ታደርጋት ነበር ? ለምን ?

# ገበሬና ነብር

ብአንድ መንደር ውስጥ የሚኖር አንድ ገበሬ ነበር ። አንድ ቀን እርሻ ሲያርስ ነብር መጣበት ። ነብሩንም አዳኞች ያባርሩት ነበር ። ነብሩም "እባክህን አንተ ገበሬ ደብቀህ አድነኝ" አለው ። ገበሬውም እሺ ብሎ ዘር እመጣበት ስልቻ ውስጥ ደበቀው ። አዳኞቹም ገበሬው አጠገብ ደረሱና "አንድ ነብር በዚህ ሲያልፍ አይተሃል ?" ብለው ጠየቁት ። ገበሬውም "እኔ አላየሁም" ብሎ መለሰላቸውና አዳኞቹ ነብሩን ፍለጋ ወደ ጫካ ሄዱ ።

በኋላ ገበሬው ነብሩን "ሰዎቹ ርቀው ስለሄዱ አያዩህምና ከስልቻዬ ውጣና ሂድ" አለው ። ነብሩም አሁን በጣም ስለራበኝ የምበላው ካላገኘሁ አልሄድም" አለው ። ገበሬውም "ታዲያ ምግብ አልያዝኩም ምን ትበላ ነው ?" አለው ። ነብሩም "አንተን እበላለሁ" አለው ።

ገበሬውም "ይህንንስ ካልህ ጓደኞችህ ይፍረዱኝ" አለው ። በዚህም ተስማምተው ፍርድ ጥየቃ ሄዱ ። ዝንጀሮ ፤ ፍየል ፤ ውሻና ጅብ በገበሬው ፈረዱበት ። ጦጣ ግን "እንዴት እንደ አዳንከው አሳየኝ" ብላ ጠየቀችው ። ገበሬውም ነብሩን እስልቻው ውስጥ አግብቶ አሰረና አሳያት ። ጦጣም ደብድቦ እንዲገድለው ለገበሬው በምልክት ነገረችው ። ገበሬውም በያዘው ዱላ ነብሩን ደብድቦ ገደለው ።



ሙ ል ሙ ያ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ገበሬው እርሻ ሲያርስ ምን መጣበት ?

ሀ/ ጅብ

ለ/ አህያ

ሐ/ ነብር

መ/ አንበሳ

፪/ ነብሩ ገበሬውን ምን አለው ?

ሀ/ ግደለኝ

ለ/ አድነኝ

ሐ/ ደብቀኝ

መ/ እሠረኝ

፫/ ገበሬው አዳኞቹን ምን አላቸው ?

ሀ/ ነብሩን አይቻለሁ

ለ/ ነብሩን ደብቄዋለሁ

ሐ/ ነብሩን አላየሁም

መ/ ነብሩን ገድዬዋለሁ

፬/ ሰዎቹ ርቀው ከሄዱ በኋላ ገበሬው ነብሩን ምን አለው ?

ሀ/ ከስልቻዬ ውጣና ሂድ

ለ/ ስልቻዬን ብላ

ሐ/ በስልቻዬ ውስጥ ተቀመጥ

መ/ ስልቻዬን ያዝና ሂድ

፭/ ገበሬውና ነብሩ ፍርድ ጥያቄ ለምን ሄዱ ?

ሀ/ ገበሬው አፉን ስለያዘው

ለ/ ገበሬው ነብሩን ስለደበደበው

ሐ/ ነብሩ ገበሬውን እበላለሁ ስላለ

መ/ ነብሩ አዳኞቹን ስለፈራ

፮/ በገበሬው ላይ እነማን ፈረዱ ?

ሀ/ ዝንጀሮ ፣ ፍየል ፣ በግ ፣ አህያ

ለ/ አህያ ፣ ዝንጀሮ ፣ ጅብ ፣ ፍየል

ሐ/ ዝንጀሮ ፣ ፍየል ፣ ውሻ ፣ ጅብ

መ/ ዝንጀሮ ፣ ፍየል ፣ ጦጣ ፣ ጅብ

፯/ ጦጣ ለማን ፈረደች ?

ሀ/ ለገበሬው

ለ/ ለነብሩ

ሐ/ ለአዳኞቹ

መ/ ለዝንጀሮዋ

፰/ ጦጣ ገበሬውን ምን ጠየቀችው ?

ሀ/ ነብሩን እንዴት እንደያዝሽው አሳየኝ

ለ/ ነብሩን እንዴት እንዳገኘሽው አሳየኝ

ሐ/ ነብሩን እንዴት እንዳሰርሽው አሳየኝ

መ/ ነብሩን እንዴት እንዳዳንሽው አሳየኝ

፱/ ገበሬው ነብሩን በምን ገደለው ?

ሀ/ በጦር

ለ/ በዱላ

ሐ/ በጐራዴ

መ/ በቢላዋ

የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ በአንድ . . . . . . . . ውስጥ የሚኖር አንድ . . . . . . . . . . ነበር ።
፪/ አንድ ቀን . . . . . . . . . . . . . ሲያርስ . . . . . . . . . . መጣበት ።
፫/ ነብሩንም . . . . . . . . . . . ያባርሩት ነበር ።
፬/ ነብሩም "እባክህን አንተ ገበሬ . . . . . . . . . . አድነኝ" አለው ።
፭/ ገበሬውም እሺ ብሎ . . . . . . . . . . . አመጣበት . . . . . ውስጥ ደበቀው ።
፮/ በኋላም ገበሬው ነብሩን "ሰዎቹ . . . . . . . . . ስለሄዱ አያዩህምና . . . . . . . .
ውጣና ሂድ" አለው ።
፯/ ነብሩም "አሁን በጣም . . . . . . . . የምበላው . . . . . . . አልሄድም" አለው ።
፰/ ገበሬውም ". . . . . . . . . ምግብ አልያዝኩም ምን . . . . . . . . . . ነው" አለው ።
፱/ ነብሩም "አንተን . . . . . . . . . . . ." አለው ።
፲/ "ይህንንስ . . . . . . . . . . ጓደኞችህ . . . . . . . . . . . . ." አለው ።
፲፩/ በዚህም . . . . . . . . . . . . . . . ፍርድ . . . . . . . . . . . . . ሄዱ ።
፲፪/ ጦጣ ግን "እንዴት . . . . . . . . . . . . . . . . አሳየኝ" ብላ ጠየቀችው ።
፲፫/ ነብሩን እስልቻው ውስጥ . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . . አሳያት ።
፲፬/ ጦጣም . . . . . . . . . . . . . . እንዲገድለው ለገበሬው . . . . . . . . . . ነገረችው ።
፲፭/ ገበሬውም በያዘው . . . . . . . . . . ነብሩን . . . . . . . . . . . ገደለው ።

የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ አንተ ነብሩን ብትሆን ኖሮ ከአዳኞቹ እንዴት ታመልጥ ነበር ?
፪/ አንተ ገበሬውን ብትሆን ነብሩን ምን ታደርገው ነበር ?
፫/ አንተ አዳኞቹን ብትሆን ኖሮ ምን ታደርግ ነበር ?

# ውሸታም ልጅ

ቀበሮ የበዛበት አንድ ጫካ ነበር ። በጫካውም አጠገብ አንድ መንደር ነበር ። የመንደሩ ሰዎች በጎቻቸውን ቀበሮ እንዳይበላባቸው እረኛ ቀጠሩ ። ሰዎቹም "ተጠንቅቀህ ጠብቅ ። በጎቹን የሚበላ ቀበሮ የመጣ እንደሆነ ጩኽ ፤ እኛ እንደርስልሃለን" ብለው ለእረኛው ነገሩት ።

እረኛውም በጎቹን ሊጠብቅ ወደ ጫካ እየነዳ ሄደ ። ጥቂት ቆየና "ቀበሮ ! ቀበሮ !" ብሎ ጮኸ ። ሰዎቹም ጩኸቱን ሰምተው እየሮጡ ቢደርሱ በጎቹን አዩዋቸው ። ቀበሮም አልመጣም ነበር ። በዚህ ጊዜ ልጁ በጣም ሳቀና "ቀለድኩባችሁ ። ቀበሮ አልመጣም ። በጎቹ ሁሉ አሉ" አላቸው ። ሰዎቹም ተናድደው ተመለሱ ። ልጁ በጎቹን ይዞ ማታ እቤት ገባ ።

በማግስቱ ጥዋት በጎቹን ይዞ ወደ ጫካ ሄደ ። እዚያም ትንሽ ቆይቶ "ቀበሮ ! ቀበሮ !" ብሎ ጮኸ ። የመንደሩ ሴቶች ሰሙና ዱላ ይዘው እየሮጡ ሄዱ ። ልጁም "ቀለድኩባችሁ ። ቀበሮ የለም" አላቸው ። ሴቶቹም ተናድደው ልጁን ለመምታት አባረሩት ፤ ሮጦ አመለጣቸው ።

በሌላ ቀን በጎቹን ሲጠብቅ ቀበሮ መጣበት ። ልጁም "ኡ ! ኡ ! ቀበሮ መጣ ፡ በጎቹን በላ" ብሎ ጮኸ ። ባለበጎቹም ሰምተው "ሲቀልድ ነው" ብለው ሳይሄዱ ቀሩ ። ቀበሮውም ብዙ በጎች በላ ። ልጁ ማታ እቤት ሲገባ ባለቤቶቹ በጎቻቸውን ቢቆጥሩ ጐድለው ተገኙ ። "ሌሎቹ በጎች የት አሉ ?" ቢሉት "ቀበሮ በላቸው" ብሎ ነገራቸው ። ባለበጎቹም በጣም ተናደዱና ቀጡት ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ የመንደሩ ሰዎች ለምን እረኛ ቀጠሩ ?
ሀ/ በጐቻቸውን ውሻ እንዳይበላባቸው  ሐ/ በጐቻቸው እንዳይጠፉባቸው
ለ/ በጐቻቸውን ቀበሮ እንዳይበላባቸው  መ/ በጐቻቸው እንዳይሞቱባቸው
፪/ መጀመሪያ እረኛው ለምን ጮኸ ?
ሀ/ ቀበሮ ስለመጣበት  ሐ/ ሰዎቹን ለማስደንገጥ ስለፈለገ
ለ/ ጅብ ስለመጣበት  መ/ ስለደነገጠ
፫/ ልጁ በመጨረሻ ለምን ጮኸ ?
ሀ/ ቀበሮ ስለመጣበት  ሐ/ ሰዎቹን ለማስደንገጥ ስለፈለገ
ለ/ ነብር ስለመጣበት  መ/ ስለፈራ
፬/ ባለበጎቹ የልጁን ጩኸት ሰምተው ለምን ሳይሄዱለት ቀሩ ?
ሀ/ ቀበሮውን ፈርተው  ሐ/ ቡና ሲጠጡ
ለ/ ልጁ ሲቀልድ ነው ብለው  መ/ ዱላ ሲፈልጉ
፭/ በመጨረሻ ባለበጎቹ እረኛውን ምን አደረጉት ?
ሀ/ ከሥራ አስወጡት  ሐ/ ተናደዱና ቀጡት
ለ/ እንጀራ ከለከሉት  መ/ ተቈጡት

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ

፩/ ቀበሮ . . . . . . . . . . . አንድ . . . . . . . . . . ነበር ።
፪/ የመንደሩ ሰዎች በጎቻቸውን ቀበሮ . . . . . . . . . እረኛ . . . . . . . . . . ።
፫/ በጎቹን . . . . . . . . . . . ቀበሮ የመጣ እንደሆነ . . . . . . . ፤ እኛ እንደርስ ልሃለን ብለው ለእረኛው ነገሩት ።
፬/ ሰዎቹም . . . . . . . . ሰምተው እየሮጡ ቢደርሱ በጐቹን . . . . . . . . . . . ።
፭/ የመንደሩ ሴቶች . . . . . . . . . ዱላ ይዘው . . . . . . . . . . . . ሄዱ ።
፮/ ሴቶቹም . . . . . . . . . . ልጁን ለመምታት አባረሩት ፤ ሮጦ . . . . . . . . . ።
፯/ . . . . . . . . . . . . . . ቀን በጎቹን ሲጠብቅ ቀበሮ መጣበት ።
፰/ ባለበጎቹም ሰምተው . . . . . . . . . ነው ብለው . . . . . . . . . . . . ቀሩ ።
፱/ ልጁ . . . . . . . . . እቤት ሲገባ . . . . . በጎቻቸውን ቢቆጥሩ . . . . . . ተገኙ ።
፲/ ቀበሮ . . . . . . . . . . . . . . ብሎ ነገራቸው ።
፲፩/ ባለበጎቹም በጣም . . . . . . . . . . . . ቀጡት ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ የበጎቹ ጌታ አንተ ብትሆን ኖሮ ልጁን ምን ታደርገው ነበር ?
፪/ ከእረኛው ሥራ የጠላኸው ምንድነው ? ለምን ?

# ዶሮዎች ለምን መሬት ይጭራሉ ?

ዱሮ አሞራዎች መብረር ስለማይችሉ ከዶሮዎች ጋር ወዳጅ ነበሩ ። ከዶሮዎችም ጋር ብዙ ጊዜ በጓደኝነት ከቆየ በኋላ አንድ ቀን አሞራ ላባውን አያይዞ የሚሰፋበት መርፌ አገኘና ሰፍቶ ለመብረር ቻለ ። ዶሮዎችም ወዳጃቸው አሞራ በሰማይ ላይ ሲበር ባዩት ጊዜ እነርሱም እንደርሱ ለመብረር ፈለጉ ።

በኋላም አሞራው በርሮ ከመሬት ሲያርፍ ዶሮዎቹ "መብረር ጥሩ ነገር ነው እኛም ለመብረር እንፈልጋለን ። እባክህን መርፌውን አውሰን" ብለው ለመኑት ። በዚህ ጊዜ አሞራው "አይሆንም መርፌውን ትጥሉብኝና እንጣላለን" አላቸው ።

ዶሮዎቹም ፤ "ግዴለም መርፌው እንዳይጠፋ እንጠነቀቃለን" አሉ ። በመጨረሻም አሞራው "አደራ እንዳትጥሉብኝ ። ተጠንቅቃችሁ ያዙ ፤" አለና መርፌውን ለዶሮዎች ሰጣቸው ። ከዚያም የመጀመሪያዋ ዶሮ መስፋት ስትጀምር መርፌው ጠፋ ። የመርፌውም መጥፋት እንደተሰማ በአሞራውና በዶሮዎቹ መካከል ጥል ተነሣ ። አሞራዎቹም "መርፌው እስኪገኝ ድረስ ጠላት እንሆናለን" አሉና ዶሮዎችን እያባረሩ መግደል ጀመሩ ። ከዚያ ወዲህ አሞራዎችና ዶሮዎች ጠላቶች ሆኑ ። አሞራዎችም ዶሮዎችን ሲያገኙ ጠልፈው የሚወስዱትና ዶሮዎችም በሰማይ ላይ አሞራ ሲያዩ የሚደበቁት ስለዚህ ነው ። ዶሮዎች አሞራው ማለፉን ሲያዩ ከተደበቁበት ወጥተው መሬት መጫራቸውን ይቀጥላሉ ። መሬት የሚጭሩበትም ምክንያት የጠፋባቸውንና ከአሞራ ጋር ያጣላቸውን መርፌ ለመፈለግ ሲሉ ነው ።

## መ ል መ ጃ

ተስማሚውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ዱሮ አሞራዎችና ዶሮዎች
- ሀ/ ጠላት ነበሩ ።
- ለ/ ወዳጅ ነበሩ ።
- ሐ/ ዘመድ ነበሩ ።
- መ/ አይተዋወቁም ነበር ።

፪/ አሞራ ለመብረር እንዴት ቻለ ?
- ሀ/ አይሮፕላን ሠርቶ
- ለ/ ጃንጥላ አበጅቶ
- ሐ/ ክንፉን ሰፍቶ
- መ/ መርፌ አግኝቶ

፫/ ዶሮዎቹ አሞራውን ምን ለመኑት ?
- ሀ/ መርፌ እንዲያውሳቸው
- ለ/ ይዟቸው እንዲበር
- ሐ/ ክንፍ እንዲሰፋላቸው
- መ/ መብረር እንዲያስተምራቸው

፬/ አሞራዎችና ዶሮዎች ለምን ተጣሉ ?

ሀ/ ዶሮዎች መብረር ስላቃታቸው
ሐ/ ዶሮዎች መርፌውን ስለጣሉ
ለ/ ዶሮዎች መስፋት ስለማይችሉ
መ/ ዶሮዎች ፈሪዎች ስለሆኑ

፭/ ዶሮዎች ለምን መሬት ይጭራሉ ?

ሀ/ ከአሞራ ለመደበቅ
ሐ/ የአሞራን መርፌ ለመቅበር
ለ/ የአሞራን መርፌ ለመፈለግ
መ/ አሞራን ለመቅበር

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

፩/ ዶሮዎችም “. . . . . . . . . . . . መርፌው እንዳይጠፋ . . . . . . . . . ” አሉ ።

፪/ በመጨረሻም አሞራው “. . . . . . . . . . . እንዳትጥሉብኝ ። . . . . . . . ያዙ” አለና መርፌውን ለዶሮዎች ሰጣቸው ።

፫/ ከዚያም . . . . . . . . ዶሮ መስፋት ስትጀምር መርፌው . . . . . . . . . . ።

፬/ የመርፌውም መጥፋት . . . . . . . . . . . . . . በአሞራውና በዶሮዎቹ መካከል . . . . . . . . . . . . ተነሣ ።

፭/ አሞራዎቹም “መርፌው . . . . . . . ድረስ ጠላት እንሆናለን” አሉና ዶሮዎቹን መግደል ጀመሩ ።

፮/ ከዚያ . . . . . . . . . . . አሞራዎችና ዶሮዎች ጠላቶች ሆኑ ።

፯/ አሞራዎችም ዶሮዎችን ሲያገኙ . . . . . . . . የሚወስዱትና ዶሮዎችም በሰማይ ላይ አሞራ ሲያዩ . . . . . . . . . . . . . ስለዚህ ነው ።

፰/ ዶሮዎች አሞራው . . . . . . . . . ሲያዩ ከተደበቁበት ወጥተው መሬት . . . . . ይቀጥላሉ ።

፱/ መሬት የሚጭሩበትም ምክንያት. . . . . . . . ከአሞራ ጋር . . . . . . መርፌ ለመፈለግ ሲሉ ነው ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ አንተ አሞራውን ብትሆን ኖሮ ዶሮዎችን ምን ታደርጋቸው ነበር ?

፪/ ለአንዱ ጓደኛህ እርሳስ አውሰኸው ቢጠፋበት ምን ታደርገዋለህ ?

፫/ ከጓደኛህ የተዋስኸው መጽሐፍ ቢጠፋብህ ምን ታደርጋለህ ?

፬/ ዶሮዎች መሬት የሚጭሩት እውነት መርፌ ለመፈለግ ነው ?

# አየለና ከበደ

አየለና ከበደ ጓደኞሞች ነበሩ ። ትምህርት ቤት አብረው ይሄዳሉ ። አብረው ይጫወታሉ ። ትምህርታቸውንም አብረው ያጠናሉ ። ከበደና አየለ ሁልጊዜ አብረው ይውላሉ ።

አንድ ቀን ከበደና አየለ ከአንድ ዛፍ ሥር ተቀምጠው ሲጫወቱ ከበደ "አንድ ትልቅ ቤት የሚያህል ሣጥን እቤታችን አለ" አለ ።

አየለ ደግሞ ፤ "እኛ ቤት በርሜል የሚያህል ብርጭቆ አለ" አለው ።

ከበደም ይህን ከሰማ በኋላ ሌላ የሚበልጥበትን ነገር ፈለገ ። ሲያስብ ቆይቶ አንድ ነገር አገኘ ። "እኛ ቤት አንድ ትልቅ ተራራ የሚያህል ከበሮ አለ ። ከበሮውም ላይ ሃያ ሰዎች ሊጨፍሩበት ይችላሉ ። ከበሮውም ሲመታ ድምጹ ከሩቅ ይሰማል" ብሎ ነገረው ።

አየለም ከበደ የተናገረውን ሁሉ አዳምጦ ። "እቤትህ ጥሩ ከበሮ አለ ። እኔ ቤት ደግሞ በጣም ትልቅ ፍየል አለ ። ፍየሉ ትልቅ መኪና በእግሮቹ መካከል ሊያሳልፍ ይችላል" ብሎ ነገረው ።

ከበደም ይህን ሰምቶ ሣቀና "ይህን ያህል ትልቅ ፍየል አይቼ ስለማላውቅ የምትነግረኝ ሁሉ ውሸት ነው" አለው ።

አየለም "እንደዚህ ዓይነት ፍየል ከሌለ ተራራ የሚያህል ከበሮ እንዴት ሊኖር ይችላል ? ከበሮ የሚሠራው ከእንጨትና ከቆዳ መሆኑን አታውቅም መሰለኝ" ብሎ መለሰለት ።

ከዚህ በኋላ ከበደና አየለ በዛፍ ሥር ቁጭ ብለው በተነጋገሩት ነገር እየሣቁ ወደ የቤታቸው ሄዱ ።



# መ ል መ ጃ

የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ አየለና ከበደ ምን ነበሩ ?
ሀ/ ጠላቶች
ለ/ ጓደኞሞች
ሐ/ ወንድማማቾች
መ/ ጥለኞች

፪/ አየለ ትምህርት ቤት የሚሄደው ከማን ጋር ነው ?
ሀ/ ከወንድሙ
ለ/ ከእኅቱ
ሐ/ ከፀሐይ
መ/ ከከበደ

፫/ ከበደ ትምህርቱን የሚያጠናው ከማን ጋር ነው ?
ሀ/ ከአየለ
ለ/ ከእኅቱ
ሐ/ ከተስፋዬ
መ/ ከመኰንን

፬/ መጀመሪያ ከበደ ለአየለ ምን ነገረው ?
ሀ/ አንድ ትልቅ ቤት የሚያህል እንስራ እቤታችን አለ ።
ለ/ አንድ ትልቅ ቤት የሚያህል ብርጭቆ እቤታችን አለ ።
ሐ/ አንድ ትልቅ ቤት የሚያህል ሣጥን እቤታችን አለ ።
መ/ አንድ ትልቅ ቤት የሚያህል ወንበር እቤታችን አለ ።

፭/ አየለ ደግሞ ምን መለሰለት ?
ሀ/ እኛ ቤት በርሜል የሚያህል ብርጭቆ አለ ።
ለ/ እኛ ቤት በርሜል የሚያህል ብርሌ አለ ።
ሐ/ እኛ ቤት በርሜል የሚያህል ጠርሙስ አለ ።
መ/ እኛ ቤት በርሜል የሚያህል ሲኒ አለ ።

፮/ ከበደ ይህን ከሰማ በኋላ ለአየለ ምን ነገረው ?
ሀ/ እኛ ቤት ትልቅ ተራራ የሚያህል ከበሮ አለ ።
ለ/ እኛ ቤት ተራራ የሚያህል ጣሳ አለ ።
ሐ/እኛ ቤት ተራራ የሚያህል ታምቡር አለ ።
መ/ እኛ ቤት ተራራ የሚያህል ቆርቆሮ አለ ።

፯/ አየለ ከበደ የሚናገረውን ሁሉ ካዳመጠ በኋላ ምን አለ ?
ሀ/ ከበደን ውሸታም ነህ አለው ።
ለ/ እቤትህ ጥሩ ከበሮ የለም አለው ።
ሐ/ እኛ ቤት ያለው ፍየል ቢቆም በእግሮቹ መካከል መኪና ያልፋል ።
መ/ እኛ ቤት ያለው ፍየል ትንሽ ነው ።

፰/ ከበሮ የሚሠራው ከምንድነው ?
ሀ/ ከጨርቅ
ለ/ ከእንጨት
ሐ/ ከመስተዋት
መ/ ከወረቀት

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ አየለና ከበደ . . . . . . . . . . . ነበሩ ።
፪/ ትምህርት ቤት . . . . . . . . . ይሄዳሉ ።
፫/ አንድ ትልቅ ቤት . . . . . . . . . . . ሣጥን . . . . . . . . . . አለ ።
፬/ እኛ ቤት . . . . . . . . . . . የሚያህል . . . . . . . . . . አለ ።
፭/ ከበደም ይህን . . . . . . . . . . በኋላ ሌላ . . . . . . . . . . . . . ነገር ፈለገ ።
፮/ አንድ ትልቅ . . . . . . . . . . . . . . የሚያህል . . . . . . . . . . . . . . አለ ።
፯/ ከ . . . . . . . ላይ . . . . . . . . . . . . . ሰዎች . . . . . . . . . . . ይችላሉ ።
፰/ . . . . . . . . . . . . . . ሲመታ . . . . . . . . . . ከሩቅ ይሰማል ።
፱/ አየለም ከበደ . . . . . . . . . . ሁሉ . . . . . . . . . . . . ።
፲/ ፍየሉ . . . . . . . . . ትልቅ መኪና በእግሮቹ . . . . . . ሊያሳልፍ ይችላል ።
፲፩/ ይህን ያህል ትልቅ ፍየል . . . . . . . . ስለማላውቅ የምትነግረኝ ሁሉ . . . . ነው ።
፲፪/ ከበደና አየለም . . . . . . ሥር ቁጭ ብለው . . . . . . . . ነገር እየሳቁ ወደየቤታቸው ሄዱ ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ያንተ ጓደኛ ማን ነው ?
፪/ ከጓደኞችህ ጋር የዚህ ዓይነት ጨዋታ ተጫውተህ ታውቃለህ ?

# ሽማግሌው ገበሬና ወጣቱ ሹም

አንድ ቀን ጠዋት አንድ ሽማግሌ ገበሬ የፍሬ ዛፍ ለመትከል ይቆፍሩ ነበር ። አውሬ ለማደን የሚሄድ አንድ ወጣት ሹም በፈረስ እየጋለበ መጣና እሽማግሌው ገበሬ አጠገብ ሲደርስ ቆሞ ይመለከት ጀመር ። ቀጥሎም "አባቴ ! ዕድሜዎ ምን ያህል ነው ?" ሲል ጠየቃቸው ። ሽማግሌውም "ሰማንያ ዓመቴ ነው" ብለው መለሱለት ። ሹሙም "ወደፊት ስንት ዓመት ይኖራሉ ?" ሲል እንደገና ጠየቃቸው ። ሽማግሌ ውም "ይህ በእግዜር እጅ ያለ ነገር ነው" አሉት ።

እንደገና ደግሞ ሹሙ "ይህ የሚተክሉት ዛፍ በስንት ዓመቱ ፍሬ ያፈራል ?" ሲል ጠየቃቸው ። ሽማግሌውም "በኻያ ዓመቱ ሳያፈራ አይቀርም" ሲሉ መለሱ ለት ። ሹሙም "ኻያ ዓመት !" ብሎ ጮኸ ፤ ቀጥሎም እየሳቀ ፤ "እንግዲያማ ሞኝ ሆነዋላ !" አላቸው ። ሽማግሌውም ፤ "እንደምን ጌታዬ ?" ሲሉ ጠየቁት ። "ፍሬ ውን ሊበሉ የማይደርሱበትን ዛፍ በመትከል መድከምዎ ነዋ !" ሲል መለሰላቸው።

በዚህም ጊዜ ሽማግሌው ፤ "ይህ ሞኝነት አይደለም ጌታዬ !" አሉና ፤ "አባ ቴና ከርሱ በፊትም የአባቴ አባት አያቴ የተከሉትን ዛፍ ፍሬ በልቼአለሁ ። ስለ ዚህ እኔም ልጆቼና የልጅ ልጆቼ ፍሬውን እንዲበሉ ዛፍ ብተክል ሞኝነት አይደ ለም" አሉት ።

ሹሙም ከሽማግሌው ገበሬ ይህን ቃል በመስማቱ ደስ አለውና "ብልሁ ሽማ ግሌ ሆይ ! ጥሩ መልስ ሰጡኝ ። ከእርስዎም ጋር በመነጋገሬ ጥሩ ትምህርት አግኝ ቻለሁ" ብሎ ሽማግሌውን ገበሬ ለማስደሰት ገንዘብ ሰጣቸውና ሔደ ።

ሽማግሌው ገበሬም በጣም ደስ አላቸው ። ከዚያም "ይህ ወጣት ሹም ዛፎቹ ምን ያደርጉልሃል ሲለኝ ይኸው አሁኑኑ የገንዘብ ፍሬ መስጠታቸው አልገባውም መሰለኝ" አሉና የፍሬ ዛፍ መትከላቸውን ቀጠሉ ።

## መ ል መ ጃ

የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ የአውሬ አደን ጥቅሙ ምንድነው ?
፪/ አውሬ የሚያድኑ ሰዎች እንዴት ያሉ ናቸው ?
፫/ የፍሬ ዛፍ የሚባሉት የትኞቹ ናቸው ?
፬/ ከአንድ ጓደኛህ ጋር ሽማግሌውና ሹሙ ያሉትን ሁሉ ተነጋገሩ ።

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

፩/ አንድ ቀን . . . . . . አንድ ሽማግሌ ገበሬ የፍሬ ዛፍ ለመትከል . . . . . ነበር ።
፪/ አውሬ . . . . . . . . . . የሚሄድ አንድ ወጣት . . . . . . . . በፈረስ . . . . . . . .
መጣና ሽማግሌው ገበሬ አጠገብ ሲደርስ ቆሞ . . . . . . . . . . . ጀመር ።
፫/ ቀጥሎም "አባቴ ! . . . . . . . . . . ያን ያህል ነው ?" ሲል . . . . . . . . . . ።
፬/ ሽማግሌውም " . . . . . . . . . . . . ዓመቴ ነው" ብለው . . . . . . . . . ።
፭/ ሹሙም " . . . . . . . . ስንት ዓመት . . . . . . ?" ሲል . . . . . . . . ጠየቃቸው ።
፮/ ሽማግሌውም "ይህ . . . . . . . . . . እጅ ያለ ነገር ነው" አሉት ።
፯/ እንደገና ደግሞ ሹሙ "ይህ . . . . . . . ዛፍ በስንት ዓመቱ ፍሬ . . . . . . . . . ?"
ሲል ጠየቃቸው ።
፰/ ሽማግሌውም " . . . . . . . . ዓመቱ ሳያፈራ አይቀርም" ሲሉ መለሱለት ።
፱/ ሹሙም " . . . . . . . . ዓመት !" ብሎ ጮኸ ።
፲/ ቀጥሎም . . . . . . . . . . "እንግዲያማ ሞኝ . . . . . . . . . . !" አላቸው ።
፲፩/ ሽማግሌውም " . . . . . . . . . ጌታዬ ?" ሲሉ ጠየቁት ።
፲፪/ "ፍሬውን . . . . . . ዛፍ በመትከል . . . . . . . . ነዋ !" ሲል መለሰላቸው ።

# የያሬድና የለማ ታሪክ

ያሬድ የሚባል አንድ ተማሪ ነበር ። እሱም ትምህርት ስለማይገባው በጣም ተናድዶ አንድ ዛፍ ሥር ተቀመጠ ። በኋላም አንድ ትል እዛፉ ላይ ሲወጣ አየ ። ትሉ ትንሽ እንደወጣ አቃተውና ወደቀ ። ከዚያም ትሉ እንደገና ሲወጣ ወደቀ ። በሦስተኛው ጊዜ ግን ወጣ ። ያሬድም ይህን ዓይቶ እንደገና ትምህርቱን ጀመረና ጐበዝ ሆነ ።

ለማ የሚባል ልጅ ደግሞ ያደረገውን ታውቃላችሁ ?

ለማ የሁለተኛ ክፍል ተማሪ ነው ። ትምህርት ቤት ገብቶ ሁለት ዓመት ተማረ ። የአማርኛ ንባብና ጽሕፈት ይችላል ። ኳስ ጨዋታ ይወዳል ። በሩጫ ሁል ጊዜ አንደኛ ይሆናል ።

ለማ ብዙ ጓደኞች አሉት ። ከበደ ፤ ሐጐስ ፤ ደበሌ ፤ መሐመድ ፤ ጊሩት ጓደኞቹ ናቸው ። ከበደ ሥዕል ይችላል ። የሰው ሥዕል ፤ የበሬ ሥዕል ፤ የቤት ሥዕል ፤ ይሥላል ። ለማ የከበደን ሥዕሎች አይቶ በጣም ደስ አለው ። እሱም ሥዕል ለማወቅ እፈልጋለሁ ብሎ መሣል ጀመረ ። የለማ ሥዕል እንደ ከበደ ሥዕል ጥሩ አልሆነም ። ስለዚህ ለማ ሥዕል መሣል አልችልም ብሎ ተወ ።

አንድ ቀን ለማና ጓደኞቹ በሩጫ ተወዳደሩ ። ውድድሩን ሲጨርሱ እዛፍ ሥር ተቀመጡ ። ለማ አንድ ትል እዛፉ ላይ ሲወጣ አየ ። ትሉም መውጣት አቅቶት ወደቀ ። በዚህ ዓይነት ትሉ ስድስት ጊዜ ከዛፉ ላይ ወድቆ በሰባተኛው ወጣና የዛፉን ፍሬ በላ ።

ለማ የትሉን ጉብዝና አየ ። ማታ እቤቱ ገብቶ ሥዕል መሣል ጀመረ ። ከብዙ ጊዜ ልምምድ በኋላ በጣም ጥሩ ሠዓሊ ሆነ ።



# መልመጃ

የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ለማ
ሀ/ ገበሬ ነው
ለ/ ነጋዴ ነው
ሐ/ ተማሪ ነው
መ/ አስተማሪ ነው

፪/ ስንት ዓመት ተማረ ?
ሀ/ አንድ
ለ/ ሁለት
ሐ/ ሦስት
መ/ አራት

፫/ ለማ ምን ይችላል ?
ሀ/ ኳስ ጨዋታ
ለ/ ሩጫ
ሐ/ የአማርኛ ንባብ
መ/ የአማርኛ ንባብና ጽሕፈት

፬/ ለማ ምን ይወዳል ?
ሀ/ ኳስ ጨዋታ
ለ/ ሩጫ
ሐ/ ዝላይ
መ/ ምንም አይወድም

፭/ ለማ አንደኛ የሚወጣው በምንድን ነው ?
ሀ/ በኳስ ጨዋታ
ለ/ በሩጫ
ሐ/ በዝላይ
መ/ በትምህርት

፮/ የለማ ጓደኞችውድድሩን ሲጨርሱ ወዴት ሄዱ ?
ሀ/ ወደቤታቸው ሄዱ
ለ/ ድንጋይ ላይ ቁጭ አሉ
ሐ/ እዛፍ ሥር ቁጭ አሉ
መ/ እዛፍ ሥር ቆሙ

፯/ የለማ ጓደኞች ስንት ናቸው ?
ሀ/ ሁለት
ለ/ ሦስት
ሐ/ አራት
መ/ አምስት

፰/ ከበደ ምን ይችላል ?
ሀ/ ኳስ ጨዋታ
ለ/ ዝላይ
ሐ/ ሥዕል
መ/ ሩጫ

፱/ ለማ ያየው ትል ከዛፍ ላይ ስንት ጊዜ ወደቀ ?
ሀ/ አንድ ጊዜ
ለ/ ሦስት ጊዜ
ሐ/ ስድስት ጊዜ
መ/ አምስት ጊዜ

፲/ ትሉ እዛፍ ላይ የወጣው በስንተኛው ጊዜ ነው ?
ሀ/ በአራተኛው
ለ/ በአምስተኛው
ሐ/ በስድስተኛው
መ/ በሰባተኛው

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ ለማ የሁለተኛ ............... ............... ነው ።
፪/ ለማ ትምህርት ቤት .......... ....... ዓመት ተማረ ።
፫/ ............. ሥዕል ይችላል ።
፬/ የለማ ሥዕል እንደ ከበ ........ ጥሩ .......... ።
፭/ ስለዚህ ለማ ሥዕል ............... .......... ብሎ ተወ ።
፮/ አንድ ቀን ለማና ........... በሩጫ .......... ።
፯/ ............. ሲጨርሱ እዛፍ ሥር .......... ።
፰/ በዚህ ዓይነት ትሉ ......... ጊዜ ከዛፍ ላይ ወድቆ .......... ወጣና የዛፉን ፍሬ በላ ።
፱/ ለማ የትሉን ............. አየ ።
፲/ ማታ እቤቱ ገብቶ ......... .......... ጀመረ ።
፲፩/ ከብዙ ጊዜ ............ በኋላ በጣም ጥሩ .......... ሆነ ።

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ለማ ሥዕል መሣል አልችልም ብሎ ትቶ ነበር ። በኋላ የትሉን ጉብዝና አይቶ ሥዕል መሳል ጀመረና ጥሩ ሠዓሊ ሆነ ። አንተ አልችልም ብለህ የተውከው ነገር አለ ? እስቲ ደጋግመህ ሞክረው ። ልትሠራው ትችላለህ ።
፪/ የለማን ታሪክ ታውቃለህ ? እስቲ ለጓደኞችህ ንገራቸው ።

# አንበሳና ጦጣ

አንድ አንበሳ በጣም ታመመና ሦስት ቀን ሙሉ ከዋሻው ሳይወጣ ዋለ ። በጫካው ውስጥ ያሉት አውሬዎች ሁሉ እየተመላለሱ እንዲጠይቁት ላከባቸው ።

ብዙ አውሬዎች እየመጡ ጠየቁት ። ከጠያቂዎቹ መካከል አንዳንዶቹ የመጡት ስለፈሩት ነበር ። ሌሎቹ ደግሞ ስላዘኑለት ነው ። አንበሳው መጥተው የጠየቁትን ሁሉ አመሰገናቸው ።

ጦጣ መጥታ ስላልጠየቀችው እንድትመጣ ላከባት ። ጦጣም የአንበሳውን መልእክት ሰምታ ለመጠየቅ ወደ አንበሳው ዋሻ ሄደች ። አንበሳውም ጦጣዋን ሲያይ በጣም ደስ አለው ። ጦጣም "እግዚአብሔር ይማርዎ" ብላ ከዋሻው በር ላይ ቆመች ። አንበሳውም "በጣም ታምሜአለሁ ፡ እባክሽን ወደዋሻው ውስጥ ገብተሽ የምነግርሽን ስሚኝ" አላት ።

ጦጣዋም "በጣም መታመምዎን ሰምቻለሁ ። ወደዋሻው ውስጥ ግን አልገባም" አለችው ። አንበሳውም "ለምን አትገቢም ?" ብሎ ጠየቃት ።

ጦጣዋም "የጠየቁዎ አውሬዎች ብዙ ሲሆኑ ወደ ዋሻው ውስጥ ገብተው የወጡ የሉም ። ስለዚህ መግባት እፈራለሁ" አለችው ።

አንበሳውም በጦጣዋ ብልጠት ተገርሞ "እንዴት አወቅሽ ?" ብሎ ጠየቃት ።

ጦጣዋም "የጠየቁዎ አውሬዎች ፋና የሚያሳየው ወደ ውስጥ መግባታቸውን እንጂ ወደ ውጭ መመለሳቸውን ስላልሆነ ነው" አለችው ።

አንበሳውም ጦጣዋ ሊበላት ማሰቡን ስላወቀችበት በጣም ተናደደ ። ዘሎ ለመያዝ ቢያስብም በሽታው ስላደከመው አልቻለም ። በመጨረሻም ጦጣዋ "እግዚአብሔር ይማርዎ" ብላ ወደቤትዋ ተመለሰች ።

## መ ል መ ጃ

### የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ የታመመው ማን ነው ?

ሀ/ አንበሳ　　ሐ/ ጦጣ

ለ/ አራዊት　　መ/ የታመመ የለም

፪/ አንበሳው ስንት ቀን እዋሻ ውስጥ ዋለ ?

ሀ/ አንድ ቀን　　ሐ/ ሦስት ቀን

ለ/ ሁለት ቀን　　መ/ አራት ቀን

፫/ አንበሳው መጥተው የጠየቁትን ሁሉ ምን አደረጋቸው ?

ሀ/ በላቸው
ለ/ ሰደባቸው
ሐ/ ተቈጣቸው
መ/ አመሰገናቸው

፬/ አንበሳውን የጠየቁት ስለምን ነበር ?

ሀ/ ስለፈሩት
ለ/ ስለሚወዳቸው
ሐ/ ስለበላቸው
መ/ ስላገኘ

፭/ አንበሳውን ያልጠየቀው ማን ነው ?

ሀ/ ነብር
ለ/ ፍየል
ሐ/ አህያ
መ/ ጦጣ

፮/ አንበሳውን የጠየቁት አራዊት የተመለሱት ከየት ነው ?

ሀ/ ከውጭ
ለ/ ከዋሻው ውስጥ ገብተው
ሐ/ ከጫካ
መ/ ካፋፍ

፯/ አንበሳው በጦጣዋ ለምን ተናደደ ?

ሀ/ ስላልጠየቀችው
ለ/ ሊበላት ማሰቡን ስላወቀችበት
ሐ/ ስለደፈረችው
መ/ ስላልገባች

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ አንድ አንበሳ በጣም . . . . . . . . . ሦስት ቀን . . . . . . . . . ከዋሻው ሳይ ወጣ ዋለ ።

፪/ በጫካው ውስጥ ያሉት . . . . . . . . ሁሉ . . . . . . እንዲጠይቁት ላከባቸው ።

፫/ ብዙ . . . . . . . . . . . . . እየመጡ ጠየቁት ።

፬/ ከጠያቂዎች መካከል አንዳንዶቹ የመጡት . . . . . . . ነበር ፤ ሌሎቹ ደግሞ . . . . . . . . . . . . ነው ።

፭/ አንበሳው መጥተው የጠየቁትን ሁሉ . . . . . . . . . . ።

፮/ ጦጣ መጥታ . . . . . . . . . . . . እንድትመጣ . . . . . . . . . . ።

፯/ ጦጣም "እግዚአብሔር . . . . . . . . . ." ብላ ከዋሻው በር ላይ ቆመች ።

፰/ አንበሳው "በጣም . . . . . . . . ፤ ወደዋሻው ውስጥ ገብተሽ . . . . . .ስሚኝ" አላት ።

፱/ ጦጣዋም "በጣም . . . . . . . . . . ሰምቻለሁ ። ወደዋሻው ውስጥ ግን . . . . . አለችው ።

፲/ "የጠየቁዎ አራዊት ሁሉ . . . . . . . . . . . . ከውጭ ነው ። እዋሻው ውስጥ . የወጡ የሉም ። ስለዚህ . . . . . . . . . እፈራለሁ ።

፲፩/ አንበሳው ጦጣዋ ሊበላት . . . . . . . . . . ስላወቀችበት በጣም ተናደደ ።

፲፪/ ዘሎ ለመያዝ . . . . . . . . . . በሽታው . . . . . . . . . . . አልቻለም ።

፲፫/ በመጨረሻም ጦጣዋ "እግዚአብሔር . . . . . . . . " ብላ ወደቤትዋ . . . . . ።

የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ አንበሳው ጦጣዋን ለምን ግቢ ያላት ይመስልሃል ?

፪/ ጦጣዋ እውስጥ የገቡት ያለመውጣታቸውን በምን አወቀች ?

፫/ የምትፈራውን ወይስ የምትወደውን ነው የምትጠይቀው ? ለምን ?

፬/ አንተ አንበሳውን ብትሆን ኖሮ ጦጣዋን ምን ታደርጋት ነበር ?



# የከተማና የአገር ቤት አይጥ

ሁለት የሚዋደዱ አይጦች ነበሩ ። አንዱ በከተማ ሲኖር ሌላው አገርት ቤት ይኖ ራል ። አንድ ቀን መንገድ ላይ ተገናኙና የአገር ቤቱ አይጥ የከተማውን አይጥ እን ዲህ አለው ፤ "እባክህን ወደ አገር ቤት ናና ቤቴን እይልኝ" የከተማውም አይጥ "እሺ ደስ ይለኛል" አለው ።

ከዚህ በኋላ አንድ ቀን የከተማው አይጥ ወዳገር ቤት ሔዶና ከወዳጁ ጋር ተገ ናኘ ፤ ወዳጁም ወደቤቱ ይዞት ሔዶ ጥሩ ምግብ አቀረበለት ። በዚህም ጊዜ የከተማው አይጥ ፤ "ይህ ምግብ ጥሩ አይደለም ፤ ደግሞ በዚህ መጥፎ ጉድጓድ ውስጥ ለምን ትኖ ራለህ ? ወደ ከተማ መጥተህ መኖር ይሻልሃል ፤ ከተማ ብትመጣ ጥሩ ቤት ውስጥ ትቀ መጣለህ ፤ ጥሩ ምግብ ትበላለህ ፤ እስቲ ወደ ከተማ መጥተህ የእኔን ቤት እየው ።" አለው ።

የአገር ቤቱ አይጥም "ከተማ እንደዚህ ጥሩ ነው ? እኔ ደግሞ ከባላገሩ የሚበልጥ ያለ አይመስለኝም ነበር ። እስቲ ያንተን ቤት መጥቼ አየውና እንመካከራለን" አለው ።

የአገር ቤቱ አይጥም ጥቂት ቀን ከቆየ በኋላ ወደ ከተማው አይጥ ቤት ሄደ ። ቤቱም በጣም ጥሩ ነበር ፤ ጥሩ ምግብም ቀረበላቸው ። ነገር ግን መብላት እንደጀመሩ ጩኸት ሰሙ ። ቀጥሎም የከተማው አይጥ "ሩጥ ! ሩጥ ! ድመት መጣ" ሲል ጮኸ ። በዚህም ጊዜ ሁለቱም አይጦች ምግባቸውን ጥለው ሮጠው ሄዱና ተደበቁ ።

ድመቱም ሳያገኛቸው ቀረ ። ከጥቂት ጊዜ በኋላ አይጦቹ ከተደበቁበት ወጡ ፤ እንደወጡም የአገር ቤቱ አይጥ "በከተማ ውስጥ መኖሩን አልወደድሁትም ፤ እኔ የም ወድደው በሜዳ መኻከል በሚገኘው ጉድጓድ ውስጥ መኖር ነው ። እዚያ እንዲህ ያለ ሥጋት የለም ። ስለዚህ ሁልጊዜ እየፈራሁ እዚህ ከመኖር አገር ቤት ያለሥጋት መኖር ይሻለኛል" ብሎት ወደ ቤቱ ተመለሰ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ከከተማና ከባላገር ኑሮ የትኛውን ትመርጣለህ ? ለምን ?
፪/ ሰው ቤት እንግድነት ብትጠራ ቤቱና ምግቡ መጥፎ ነው ብለህ ትነግረዋለህ ? ለምን ?
፫/ ሰው የሚገባበዘው ለምንድነው ?

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

ከዚህ በኋላ አንድ ቀን ....... አይጥ ወዳገር ቤት ሄደና ......... ተገናኘ ። ወዳጁም ወደቤቱ ........... ሄዶ ምግብ .......... ። በዚህም ጊዜ የከተማው አይጥ "ይህ ......... ጥሩ አይደለም ። ደግሞ በዚህ መጥፎ ....... ውስጥ ለምን ............. ። ወደ ከተማ መጥተህ .......... ይሻልሃል ። ከተማ ........ ጥሩ ቤት ውስጥ ትቀመጣለህ ። ጥሩ ምግብ .......... ። እስቲ ወደ ከተማ መጥተህ የእኔን ቤት ......." አለው ። የአገር ቤቱ አይጥም "ከተማ ......... ጥሩ ነው ? እኔ ደግሞ ............. የሚበልጥ ያለ .......... ነበር ። እስቲ ያንተን ቤት መጥቼ አየውና ................" አለው ።



# አየለና አንዲት ወፍ

ቤቱ እሜካ አጠገብ የሆነ አየለ የሚባል ልጅ ነበረ ። አየለም እሜካው ውስጥ የሚኖሩትን ልዩ ልዩ ዓይነት ወፎች መያዝ ይወድ ነበር ። አንድ ቀን አንድ የምታምር ወፍ በአንድ ዛፍ ላይ አርፋ አየ ። አየለም ወፍዋ በጣም ደስ ስላለችው ወደ ዛፉ ተጠግቶ ያያት ጀመር ። ወፍዋ ግን አየለን ስላላየችው ከአንዱ ቅርንጫፍ ወደሌላው መዝለል ጀመረች ። በመጨረሻም አየለ ሊደርስባት እሚችለው ቅርንጫፍ ላይ ቁጭ አለች ።

አየለም ቀስ ብሎ ወፍዋን ያዛት ። በጣም ደስ አለው ። አንድ ጊዜ በግራ እጁ፥ አንድ ጊዜ በቀኙ እየያዘ ያያት ጀመረ ። የወፍዋ ላባ ቀይ ፤ አረንጓዴ ፤ ሰማያዊ ፤ ብጫ ነበር ። በኋላም አየለ "አንቺ ወፍ እንዴት ታምሪያለሽ" አላት ።

ወፍዋም "እኔ በጣም አላምርም ። ግን ብትለቀኝ በትምህርት ጉበዝ የምትሆንበትን ብልሃት እነግርህ ነበር" አለችው ።

አየለም "በትምህርት ጉበዝ የምሆንበትን ብልሃት ከነገርሽኝ እለቅሻለሁ" አላት ።

ወፍዋም "የምነግርህን በደንብ አዳምጠኝ" አለችውና የሚከተሉትን ነገረችው ።

አንደኛ ፤ ሁልጊዜ ጤንነትህን ጠብቅ ። እጅህን ፤ እግርህን ፤ ፀጉርህንና ገላህን ታጠብ ። ልብስህንም እጠብ ። ጥርስህን አጽዳ ።

ሁለተኛ ፤ ደብተሮችህንና መጽሐፍህን በጥንቃቄ ያዝ ። ትምህርትህን በርትተህ አጥና ።

ሦስተኛ ፤ በዕረፍት ጊዜህ ወላጆችህን እርዳ ። የሚያዙህንም ሥራ ሁሉ ሥራ ። ሥራ በሌለህ ጊዜ መጽሐፍ አንብብ ወይም ተጫወት ።

አየለም "በጣም አመሰግንሻለሁ" አለና ወፍዋን ለቀቃት ። ከዚያን ቀን ጀምሮ አየለ ወፍዋ እንደነገረችው አደረገና በትምህርቱ በጣም ጉበዝ ሆነ ። አመሉም ጥሩ ሆነ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ የአየለ ቤት የት ነው ?
- ሀ/ አንድ ጫካ አጠገብ
- ሐ/ አንድ ወንዝ አጠገብ
- ለ/ አንድ ተራራ ሥር
- መ/ አንድ ወርካ ሥር

፪/ አየለ ምን ይወድ ነበር ?
- ሀ/ እርሻ
- ሐ/ ወፍ መያዝ
- ለ/ ትምህርት
- መ/ አደን

፫/ አየለ አንድ ቀን ምን ያዘ ?
- ሀ/ ነብር
- ሐ/ የምታምር ወፍ
- ለ/ አንበሳ
- መ/ ቀበሮ

፬/ የወፍዋ ላባ ምን ዓይነት ቀለም ነበር ?
- ሀ/ ጥቁር ፥ አረንጓዴ ፥ ሰማያዊ ፥ ብጫ
- ሐ/ አረንጓዴ ፥ ሰማያዊ ፥ ብጫ ፥ ቀይ
- ለ/ አረንጓዴ ፥ ብጫ
- መ/ ወፍዋ ላባ የላትም ።

፭/ ወፍዋ ለአየለ ምን ነገረችው ?
- ሀ/ ትምህርት የሚያገኝበትን ብልሃት
- ሐ/ ሀብታም የሚያደርግ ብልሃት
- ለ/ አዳኝ የሚያደርግ ብልሃት
- መ/ ጐበዝ የሚያደርግ ብልሃት

፮/ አየለ ወፍዋን በመጨረሻ
- ሀ/ ለውሻው ሰጣት
- ሐ/ አሠራት
- ለ/ ገደላት
- መ/ ለቀቃት

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

፩/ ቤቱ ጫካ . . . . . . . . . የሆነ አየለ . . . . . . . . . ልጅ ነበረ ።

፪/ አየለም እጫካው ውስጥ የሚኖሩትን . . . . . . .  . . . . . . . . ዓይነት ወፎች መያዝ ይወድ ነበር ።

፫/ አንድ ቀን አንድ . . . . . . . . . . . . ወፍ በአንድ ዛፍ ላይ . . . . . . . . . . . አየ ።

፬/ አየለ ወፍዋ በጣም . . . . . . . . . ስላለችው ወደዛፉ . . . . . ያያት ጀመር ።

፭/ ወፍዋ ግን አየለን . . . . . . . . . ከአንድ ቅርንጫፍ . . . . . መዝለል ጀመረች ።

፮/ በመጨረሻም አየለ . . . . . . . . . ከሚችለው . . . . ላይ ቁጭ አለች ።

፯/ አንድ ጊዜ . . . . . . . . . . . እጁ አንድ ጊዜ . . . . . . እየያዘ ያያት ጀመር ።

፰/ "እኔ በጣም . . . . . . . . . . ። ግን . . . . . . . . . . በትምህርት ጐበዝ የምትሆን በትን . . . . . . . . . እነግርህ ነበር" አለችው ።

፱/ "በትምህርት . . . . . . . . . . የምሆንበትን . . . . . . . . ከነገርሽን እለቅሻለሁ ።

፲/ ከዚያን ቀን . . . . . . . . . አየለ ወፍዋ እንደነገረችው . . . . . . . . . በትምህርቱ በጣም ጐበዝ ሆነ ።

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ወፍዋ ለአየለ ምን ነገረችው ?
፪/ አንተ አየለን ብትሆን ወፍዋን ምን ታደርጋት ነበር ?
፫/ የምትፈልገውን ነገር የሚሰጥህ ብታገኝ ምን ትጠይቅ ነበር ?

# ርግብና ብራብሮ

ዱሮ የብራብሮ መልክ መጥፎ ነበር ። አንድ ቀን ብራብሮ የሚያማምሩ ላባዎች ያሉዋቸውን ወፎች አየና "ይህን የሚያምር ላባ ከየት አገኛችሁት" ብሎ ጠየቃቸው ። ወፎቹም "ርግብን ጠይቃት" ሲሉ መለሱለት ። በዚህም ጊዜ ብራብሮው "በጣም አመሰግናችኋለሁ" አለና ርግብን ሊጠይቅ ሄደ ። "ጥሩ ቀለም እንዳለሽ እባክሽን ቀቢኝ" ሲል ለመናት ።

ርግብም "ቀስተ ደመና በሰማይ ላይ በአየህ ጊዜ ተመልሰህ ና እኔም ወደ ቀስተ ደመናው አወጣሃለሁ ። ከዚያም የሚያምር ቀለም ታገኛለህ" አለችው ። ብራብሮውም በሰማይ ላይ ቀስተ ደመና ሲያይ ወደ ርግብ ተመልሶ ሄደ ። ሲሔድም ብቻውን አልሔደም ፣ የሚያምር ቀለም ለመቀባት የሚፈልጉትን ጥንዚዛዎችንም ይዞአቸው ሄዶ ነበር ።

በዚህም ጊዜ ርግቢቱ ለብራብሮውና ለጥንዚዛዎቹ እንዲህ አለቻቸው ። "ርስ በርሳችሁ ተያያዙና አንገቴ ላይ ተጠምጠሙ ። እኔም ወደ ቀስተ ደመናው ይዤ ችሁ እበርራለሁ ።"

ብራብሮውና ጥንዚዛዎቹም ርግቢቱ አንገት ላይ ተጠመጠሙ ። በዚህም ጊዜ ርግ ቢቱ ብራብሮውንና ጥንዚዛዎቹን በአንገትዋ ዙርያ አድርጋ ልዩ ልዩ ቀለም ወደ አለው ቀስተ ደመና በረረችና ቀስተ ደመናው አጠገብ ደረሰች ። በቀስተ ደመናውም ውስጥ ተዘዋወረች ። ብራብሮውና ጥንዚዛዎቹም አንገትዋን አቅፈው ነበር ። ቀስተ ደመናው አጠገብ ለጥቂት ጊዜ ከቆየች በኋላ እንደያዘቻቸው ተመልሳ ወደ መሬት ወረደች ።

መሬት ደርሰውም ቢመለከቱ ብራብሮው በጥሩ ቀለም ተዥጎርጉሮ ተገኘ ። ከጥ ንዚዛዎቹም ጥቂቶቹ ዝንጉርጉር ሆኑ ። የርግቢቱ አንገት ዙርያም ጥቁር ሆነ ይህም የሆ ነው ጥንዚዛዎቹ ርግቢቱ አንገት ላይ ሲጠመጠሙ እግራቸውን ስላልታጠቡ ነው ።





# መ ል መ ጃ

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ ብራብሮ አይተሃል ? ምን ዓይነት ቀለም አለው ?
፪/ እግራችንን ባንታጠብ ምን ጉዳት ይደርስብናል ?
፫/ ጓደኛህ አንድ ጥሩ ነገር አድርግልኝ ቢልህ ምን ታደርግለታለህ ?
፬/ ታናሽ ወንድምህ ተሸከመኝ ብሎህ ስትሸከመው ልብስህን ቢያጠፋብህ ምን ታደርገዋለህ ?
፭/ አንተስ በጭቃ ወይም በአቧራ የሰው ልብስ ብታበላሽ ምን ታደርጋለህ ?

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

፩/ ብራብሮውና . . . . . . . . ርግቢቱ አንገት ላይ . . . . . . . ።
፪/ በዚህም ጊዜ ርግቢቱ . . . . . . . . . ጥንዚዛዎቹን በአንገትዋ ላይ . . . . . . አድ ርጋ ልዩ ልዩ ቀለም ወዳለው . . . . . . . . . .  . . . . . . . በረረችና ደመናው አጠገብ ደረሰች ።
፫/ በቀስተ ደመናውም ውስጥ . . . . . . . . ።
፬/ ብራብሮውና ጥንዚዛዎችም አንገትዋን . . . . . . . . . . ነበር ።
፭/ ቀስተ ደመና አጠገብ . . . . . . . . ጊዜ ከቆየች በኋላ . . . . . . . . ተመልሳ ወደ መሬት ወረደች ።
፮/ ሙሬት . . . . . . . . . ቢመለከቱ ብራብሮው በጥሩ ቀለም . . . . . . . . ተገኘ ።
፯/ ከጥንዚዛዎቹም . . . . . . . . . . . . ዝንጉርጉር ሆኑ ።
፰/ የርግቢቱ አንገት . . . . . . . . . . .ጥቁር ሆነ ።
፱/ ይህም የሆነው ጥንዚዛዎቹ ርግቢቱ አንገት ላይ . . . . . . እግራቸውን . . . . . ነው ።

# አንድ ብልኅ ገበሬ

አንድ ብልኅ ገበሬ በአንድ አገር ውስጥ ይኖር ነበር ። ይህም ገበሬ ሰፊ መሬት ነበረው ። በጣም ጐበዝ ገበሬ ስለሆነ ለከብቶቹ ሣር የሚሆነውን ቦታ ብቻ ትቶ ሌላ ውን ያርስ ነበር ።

አንድ ዓመት ብዙ እህል ዘራና ማጨድ አቃተው ። በኋላም የሚረዳው ሰው ለመ ቅጠር ስለፈለገ ሠራተኛ እንዲጠራለት ልጁን አዘዘው ። ልጁም ሠራተኛ ጠራ ። ገበ ሬውም ማሳውን ሁሉ እያዞረ ለሠራተኛው አሳየውና እንዲያጭድለት ነገረው ።

ሠራተኛውም "እስከ ስንት ሰዓት ልጨድ ?" ብሎ ጠየቀው ። ገበሬውም "ብር ሃን እስኪጠፋ ድረስ ታጭድልኛለህ" አለው ። ሠራተኛውም "ስንት ይከፍሉኛል ?" አለው ። ገበሬውም "ልክ እኔ እንዳዘዝሁህ ከሠራህ አንድ ከረጢት እህል እከፍልሃ ለሁ" አለው ። ከዚህ በኋላ ሠራተኛው በዋጋ ተስማምቶ ሥራውን ጀመረ ።

ሰውዬው ጐበዝ ስለነበረ ቀኑን ሙሉ ሲያጭድና ሲከምር ዋለ ። የምሳ ሰዓት ሲደ ርስም ምሳውን ቶሎ በልቶ ሥራውን እንደገና ጀመረ ። በዚህ ዓይነት ሲደክም ውሎ ፀሐይዋ ስትጠልቅ ወደ ገበሬው ቤት ሄደና "ይኸው የዛሬውን ሥራ ጨርሻለሁ" አለው ። ገበሬውም ማሳውን ሄዶ አየና "የማሳው ግማሽ አልታጨደም" አለው ።



ሠራተኛውም አጨዳው ባያልቅ በውለታችን መሠረት ፀሐይዋ ጠልቃለች። ቀኑም ጨልሟል'' ብሎ መለሰለት ።

ገበሬውም መልሶ "ፀሐይዋ ጠልቃለች ። ነገር ግን የርስዋ እናት ፣ ጨረቃ ብር ሃን ልትሰጠን ወጥታለችና እርስዋ እስክትጠፋ ድረስ ማጨድ አለብህ ። ይህን ካላደረ ግህ ግን እህሉን አልሰጥህም'' አለው ። ሠራተኛውም ጉበዝ ስለነበረ ሌሊቱን ሙሉ ሲያጭድ አድሮ ሲነጋ ጨረሰ ።

ገበሬውም በጣም ደስ ስላለው "ከረጢትህን አምጣና እህሉን ልስጥህ'' አለው ። ሠራተኛው ወደቤቱ ሄዶ ትልቅ ጆንያ ይዞ መጣ ።

ገበሬውም ጆንያውን ተመልክቶ "ለምን ጆንያ አመጣህ ?'' ብሎ ጠየቀው ። ሠራተኛውም "ከረጢቱ የትልቁ ጆንያ ወንድም ስለሆነ ነው'' አለው ። ገበሬውም "ከረጢት ምን ትልቅ ወንድም አለው ?'' ቢለው ሠራተኛው "ጨረቃ የፀሐይ እናት ከሆነች ጆንያም የከረጢት ወንድም መሆን አለበት'' ብሎ መለሰለት ። በዚህ ጊዜ ገበ ሬው ምንም ሳይመልስ እህሉን በጆንያው ሞልቶ ለሠራተኛው ሰጠውና ወደ ቤቱ ሄደ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚስማማውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ገበሬው ምን ዓይነት ሰው ነበር ?

ሀ/ ሰነፍ ሐ/ ጨቅጫቃ

ለ/ ብልህ መ/ ተሟጋች

፪/ የገበሬው መሬት ?

ሀ/ ጠባብ ነበር ሐ/ ሰፊ ነበር

ለ/ ረጅም ነበር መ/ አጭር ነበር

፫. ሠራተኛውን ማን ጠራው ?

ሀ/ የገበሬው አሽከር ሐ/ የገበሬው ልጅ

ለ/ የገበሬው አሽከር ልጅ መ/ የሠራተኛው ልጅ

፬/ ገበሬው ለሠራተኛው መጀመሪያ ምን አሳየው ?

ሀ/ ማጭድ ሐ/ ክምር

ለ/ ሣር መ/ ማሳ

፭/ ገበሬው ያጨደው

ሀ/ አንድ ቀን ብቻ ነው ሐ/ አንድ ቀንና አንድ ሌሊት ነው

ለ/ ሁለት ቀን ብቻ ነው መ/ ሦስት ቀን ሙሉ ነው

፮/ ሠራተኛው እህል የወሰደው ?

ሀ/ በከረጢት ነው ሐ/ በእንቅብ ነው

ለ/ በጆንያ ነው መ/ በስልቻ ነው

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች እየሞላህ ጻፍ ።

አንድ . . . . . . . . . . ገበሬ በአንድ መንደር ውስጥ ይኖር ነበር ። ይህም ገበሬ . . . . . . . . . .መሬት ነበረው ። በጣም . . . . . . . ገበሬ ስለሆነ . . . . . . . . . . ሣር የሚሆነውን ቦታ . . . . . . . . ትቶ ሌላውን ያርሰው ነበር ።

አንድ ዓመት ብዙ እህል . . . . . . . . . . . ማጨድ አቃተው ። በኋላም ሰው ለመቅጠር ስለፈለገ . . . . . . . . . . . .እንዲጠራለት ልጁን አዘዘው ። ልጁም ሠራተኛ ጠራ ። ገበሬውም . . . . . . . . . ሁሉ እያዞረ ለሠራተኛው አሳየውና . . . . . . ነገረው ።

# ዶሮ ለምን ከሰው ጋር ትኖራለች ?

አንድ ጊዜ እጫካ ውስጥ የሰው ጫማ ወድቆ ተገኘ ። ከየት እንደመጣም የሚያውቅ አልነበረም ። በዚያም አቅራቢያ ሰው አልነበረም ። በዚያ አካባቢ የሚኖሩ እንስሳና አውሬዎች ፈጽሞ ሰው አይተው አያውቁም ።

ነገር ግን አንድ የሰው ጫማ በዚያ ጫካ ውስጥ ተገኘ ። መጀመርያ ጫማውን ያየ ውም ጅብ ነበረ ። ጅብም ያገኘው ነገር ምን እንደሆነ ማወቅ ስላቃተው አንበሳን ፤ ዝንጀሮን ፤ ቀበሮን ፤ ፍየልንና ዶሮን ጠርቶ አሳያቸው ።

በመጀመሪያም አንበሳ ጫማውን አየና "ይህ የትልቅ ዛፍ ቅርፊት ነው' አለ ። ቀጥሎም ዝንጀሮ "ይህ የብርቱካን ልጣጭ ነው" አለ ። ቀበሮ ደግሞ "ይህ ሁሉ ስህ ተት ነው ። ይህ ነገር የወፍ ጎጆ ነው ። ይህ ቀዳዳው ወፍዋ ወደ ውስጥ የምትገባበት ነው ። ይህ ጉድጓዳው ደግሞ እንቁላል የምትጥልበት ነው ። ስለዚህ ይህ በእርግጥ የወፍ ጎጆ መሆን አለበት" አለች ።

ፍየል ደግሞ "ሁላችሁም ተሳስታችኋል" አለችና ፤ ወደ ጫማ ማሠሪያው እያመ ለከተች ፤ "ይህን ረዥም ሥር ተመልከቱ ። ይህ አንድ ዓይነት አትክልት ነው" አለች ።

ሌሎቹ አውሬዎች ይህን ሲነጋገሩ አሮጊትዋ ዶሮ ትሰማ ነበር ። ዶሮዋም "ሁላ ችሁም ዝም ብላችሁ ብትሰሙኝ ይህ ነገር ምን እንደሆነ እኔ እነግራችኋለሁ ። ይህን የመሰለ ብዙ ነገር አይቻለሁ ። እሱም የሰው ጫማ ነው" አለቻቸው ።

በዚህም ጊዜ ሁሉም ብድግ አሉና "ምን ? ሰው ማለት ምንድነው ? ጫማስ ማለት ምንድነው ?" ብለው ጠየቋት ።

ዶሮዋም "ሰው ማለት ሁለት እግሮች ያሉት ነገር ነው ። ክንፍ የለውም ። አይበ ርም እንጂ እንደ ወፍ ነው ። እንደ እኛ መሄድ ይችላል ። እንደ እኛ መብላት ይች ላል ። ከምንሠራውም የበለጠ መሥራት ይችላል" አለቻቸው ። በዚህም ጊዜ ጅብ "ይህ እውነት አይደለም ሁለት እግር ብቻ ያለው አራት እግር ካለን የበለጠ መሥራት እንዴት ይችላል ?" አለ ።

በዚህም ጊዜ እዚያ የተሰበሰቡት ሁሉ "እውነት አይደለም ፤ እውነት አይ ደለም !" ሲሉ ጮኹና ፤ "እኛ እናውቃለን ፤ እንዲህ ያለ ነገር እግር ላይ አይደረግም ፤ የምትዪው ሁሉ እውነት አይደለም ፤ ውሸተኛ ከሆንሽ ከእኛ ጋር ለመኖር አትችዪም ። ስለዚህ ጫካችንን ልቀቂልን" አሉአትና ዶሮዋን ከጫካ አስወጥተው አባረርዋት ። እሷም ጫካውን ትታላቸው ከሰው ጋር መኖር ጀመረች ።

# መ ል መ ጃ

## ተስማሚውን መልስ ምረጥ ።

፩/ ጫማውን መጀመሪያ ያየው ማን ነበር ?
ሀ/ አንበሳ
ለ/ ዝንጀሮ
ሐ/ ቀበሮ
መ/ ጅብ

፪/ አንበሳ ጫማውን አይቶ ምን አለ ?
ሀ/ የወፍ ጐጆ ነው ።
ለ/ የእንጨት ቅርፊት ነው ።
ሐ/ አትክልት ነው ።
መ/ የሰው ጫማ ነው ።

፫/ ዶሮ ከጫካ ለምን ወጣች ?
ሀ/ የሰው ጫማ ስለሰረቀች
ለ/ የሰው ጫማ ስላወቀች
ሐ/ የሰው ጫማ ስላደረገች
መ/ የሰው ጫማ ስለጣለች

፬/ ዶሮ ከጫካ ወጥታ ወዴት ሄደች ?
ሀ/ ወደ ቤትዋ ገባች ።
ለ/ ከዛፍ ላይ ወጣች ።
ሐ/ ከሰው ጋር መኖር ጀመረች ።
መ/ በሰማይ ላይ ትበር ጀመር ።

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

ዶሮዋም "ሰው ማለት ሁለት . . . . . . . ያሉት ነገር ነው ። . . . . . . . . የለውም። . . . . . . . . . እንጂ እንደ ወፍ ነው ። እንደ እኛ . . . . . . . . ይችላል ። እንደ እኛ . . . . . ይችላል ። . . . . . . . . . . . የበለጠ ለመሥራት ይችላል" አለቻቸው ። በዚህም ጊዜ ጅብ "ይህ . . . . . . አይደለም ። ሁለት . . . . . . ብቻ ያለው . . . . . . . . . እግር ካለን የበ ለጠ . . . . . . . . . . . . እንዴት ይችላል ?" አለ ።

በዚህም ጊዜ እዚያ . . . . . . . . . . . . . . ሁሉ "እውነት አይደለም ! . . . . . . . . አይደለም !" ሲሉ ጮኹና "እኛ . . . . . . . . . ፣ እንዲህ ያለ ነገር እግር ላይ . . . . . . . . ፣ የምትዪው ሁሉ እውነት አይደለም ፣ . . . . . . . . . . ከሆንሽ ከእኛ ጋር . . . . . . . አትችይም ። ስለዚህ . . . . . . . . . . . ልቀቂልን" አሉአትና ዶሮዋን ከጫካ . . . . . . አባ ረርዋት ። እሷም ጫካውን . . . . . . . . . ከሰው ጋር መኖር ጀመረች ።

# የሚናገር ወፍ

"አይጠረጠርም" እያለ የሚናገር አንድ ወፍ ነበር ። ይህም ወፍ በጣም አስቸጋሪ ስለነበረ ባለቤቱ ሊሸጠው ፈለገና ወደ ገበያ ይዞት ሄደ ። የወፉ ባለቤት ወፉን በጎጆው ውስጥ እንዳደረገ አጠገቡ ቆሞ ገዢ ሲጠባበቅ ፤ ወዲያው አንድ ሰው ከትንሽ ልጅ ጋር መጣ ። ሰውየውም ሞኝ ነበረና ቆሞ ወፉን ሲመለከት ቆየ ። በዚህም ጊዜ የወፉ ጌታ "ይህን ወፍ ልትገዙ ትፈልጋላችሁ ?" አለው ። ትንሹ ልጅም "መናገር ይችላል ?" ሲል ጠየቀው ። የወፉ ጌታም "አዎ ! መናገር ይችላል ። በጣም ጐበዝ ወፍ ነው" ሲል መለሰለት ። የልጁም አባት "ጥሩ ፤ ዋጋው ስንት ነው" ብሎ ጠየቀው ። የወፉ ባለቤትም "ከነጎጆው ሠላሳ አምስት ብር ነው" አለው ።

በዚህም ጊዜ ገዢው ሰውዬ ወደ ወፉ ጎጆ መለስ አለና ፤ "አንተ ወፍ ፤ ሰላሳ አምስት ብር ታወጣለህ ?" ሲል ወፉን ጠየቀው። ወፉም ቶሎ አለና "አይጠረጠርም" ሲል መለሰለት ። በዚህም ጊዜ ሰውየው በጣም ተደስቶ ሠላሳ አምስቱን ብር ለወፉ ባለቤት ሰጠና ወፉን ይዞ ከልጁ ጋር ወደ ቤቱ ሄደ ።

እቤቱም ሲደርስ ሚስቱን ጠራና ወፉን አሳያት ፤ ሚስቱም "ይህ የሚናገር ወፍ ነው ?" አለችና ጠየቀችው ። በዚህም ጊዜ ባልየው ፤ "ጥሩ አድርጎ ይናገራል ። እስቲ አነጋግሪው" አላት ።

በዚህም ጊዜ ሴትዮዋ "አንተ ወፍ አሁን ስንት ሰዓት ነው ?" ስትል ወፉን ጠየቀችው ። ወፉም "አይጠረጠርም" ሲል መለሰላት ። በዚህም ጊዜ ሴትዮዪቱ "ምን ዓይነት መልስ ነው ? እስቲ ደግሞ እንደገና ልሞክር ፤" አለችና ወደ ትንሹ ልጅዋ እጅዋን ዘርግታ "አንተ ወፍ ይህ ልጅ ስንት ዓመቱ ነው ?" ስትል ጠየቀችው ። አሁንም ወፉ "አይጠረጠርም" ሲል መለሰላት ።

ከዚህ በኋላ ሴትዮዋ ወደ ባልዋ ዞር አለችና "ይህን ወፍ በመግዛትህ በጣም ተሞኝተሃል ?" ብላ ስትናገር ወፉ "አይጠረጠርም" ሲል ጮኸ ፤ በዚህም ጊዜ ሁሉም ሳቅ ብቻ ሆኑ ።



# መ ል መ ጃ

## የሚከተሉትን ጥያቄዎች መልስ ።

፩/ አይጠረጠርም ማለት ምን ማለት ነው ?
፪/ አንተ የወፉ ባለቤት ብትሆን ኖሮ ወፉን ትሸጠው ነበር ? ለምን ?
፫/ አንተ እንደዚህ ያለውን ወፍ ትገዛለህ ? ለምን ?
፬/ አንተ ወፉን ብትገዛ ኖሮ ምን ታደርገው ነበር ?

## የሚከተሉትን ባዶ ቦታዎች ሙላ ።

“. . . . . . . . . .” እያለ የሚናገር አንድ ወፍ ነበር ። ይህም ወፍ በጣም . . . . . . . ስለነበረ ባለቤቱ . . . . . . . . . . ፈለገና ወደ ገበያ ይዞት ሄደ ። የወፉ ባለቤት ወፉን . . . . ውስጥ እንዳደረገ አጠገቡ ቆሞ . . . . . . . . ሲጠባበቅ ወዲያው አንድ ሰው . . . . . ልጅ ጋር መጣ ። ሰውዬውም ይህን ወፍ . . . . . . . ትፈልጋላችሁ ?” አለ ። ትንሹ ልጅም “. . . . . . . . . ይችላል ?” ሲል ጠየቀው ። የወፉ ጌታም” አዎ ! . . . . . . ይችላል ። በጣም . . . . . . . . ወፍ ነው” ሲል መለሰለት ። የልጁ አባት “ጥሩ ፤ . . . . . . . ስንት ነው” ብሎ ጠየቀው ። የወፉ ባለቤትም “. . . . . . . . . ሠላሳ አምስት ብር ነው” አለው ።



**ማሳሰቢያ ።**

በተማሪው ፡ መጽሐፍ ፡ በሚገባ ፡ ለማስተማር ፡ ይቻል ፡ ዘንድ ፡ የመምህሩ ፡ መምሪያ ፡ ለአስተማሪው ፡ መሰጠት ፡ አለበት ።

ዋጋው የኢ.ት $0.30